# ምዕራፍ ፲፪

## የወልደጊዮርጊስ፣ ተቃዋሚዎች ወደ ሹመት ወዳጆች ወደ ሽረት

እንደ ኢት.አቆ ሰኞ ሚያዝያ 17 ቀን 1947 ዓ.ም በገነተ ለዑል ቤተመንግሥት ከፈነዳው ታላቅ ሹመት በኋላ፣ የጸሐፊ ትዕዛዝ ወዳጆች ሁሉ የት ይሆን መውደቂያችን? እያሉ ሲጨነቁ፣ ተቃዋሚዎች ደግሞ የትኛውን ከፍተኛ ቦታ እንሾም ይሆን? በማለት ለደስታ ሲዘጋጁ ይታዩ ነበር። ከአጅሬ ከሥልጣን መነሳት በኋላ፣ በገነተ ለዑል ቤተመንግሥት ቅጥር ግቢ ውስጥ የሚደረገው ሹመትና ሽረት ለሦስት ሳምንታት ያህል ሳያቋርጥ ቀይቷል። በዚህም አኳኋን ከጸሐፊ ትዕዛዝ ተቃዋሚዎች መካከል ከፍተኛ ሹመት የተሰጣቸው ዋና ዋናዎቹ ታላላቅ ሰዎች የሚከተሉት ነበሩ።

1. ለስድስት ዓመታት ያህል የአገር ግዛት ሚኒስትር የነበሩት ራስ አበበ አረጋይ፣ በሌፍትናንት ጄኔራል ወታደራዊ ማዕርግ፣ በአዲስ መልክ የተቋቋመው የመከላከያ ሚኒስትር፣

2. የከፋ ጠቅላይ ገዥ የነበሩት ደጃዝማች መሥፍን ስለሺ የአገር ግዛት ሚኒስትር፣

3. የሐረር ጠቅላይ ግዛት እንደራሴ የነበሩት ብላታ አየለ ገብሬ የፍርድ ሚኒስትር፣

4. የንጉሠ ነገሥቱ ልዩ ጸሐፊ የነበሩት አቶ ተፈራወርቅ ኪዳነወልድ ጸሐፊ ትዕዛዝ ተብለው የጽሕፈት ሚኒስትር፣

5. የክብር ዘበኛ ዋና አዛዥ የነበሩት ብሪጋድየር ጄኔራል ሙሉጌታ ቡሊ፣ ሜጀር ጄኔራል ተብለው የንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት የጦር ኃይሎች ጠቅላይ ኢታ ማዦር ሹም፣

6. የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር በመሆን ለሰባት ዓመታት ከወልደጊዮርጊስ ጋር የሠሩት አቶ ገብረወልድ እንግዳወርቅ ምክትል ጸሐፊ ትዕዛዝ፣

7. ብላታ ታከለ ወልደሐዋርያት በአገር ግዛት ሚኒስቴር ም/ሚኒስትር

የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወዳጆች ናቸው በመባል የሥራ ዝውውርም ሆነ ሽረት የደረሰባቸው ባለሥልጣኖች ደግሞ፣ የሚከተሉት ናቸው።

1. የጦር ሚኒስትር የነበሩት ብሪጋድየር ጄኔራል አቢይ አበበ፣ በፓሪስ የኢትዮጵያ አምባሳደር ሆኑ። ይህ ሹመት በአዋጅ ሲነገር፣ በአዲስ አበባ የተሰጠው ትችት በጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወዳጅነት ምክንያት የቀድሞው የንጉሠ ነገሥቱ አማች ወደ ግዞት ተላኩ ተብሎ ነው።

የዚህ መጽሐፍ ደራሲ እ.ኤ.አ በ1957 ዓ.ም በፓሪስ የጋዜጠኛነት ሞያ በማጠናበት ጊዜ፣ አንድ ጥሩ አጋጣሚ አግኝቼ ከጄኔራል አቢይ አበበ ጋር ስነጋገር፣ " ጌታዬ ቢፈቅዱልኝ በድፍረት አንድ ጥያቄ ማቅረብ እፈልጋለሁ " አልኳቸው። ወዲያው በሰጡኝ መልስ፣ " ... ድፍረትን ምን አመጣው? ጋዜጠኛ እኮ የሚያስበውን ሁሉ እንዲጠይቅ ይፈቀድለታል ... " አሉኝ። ወዲያው ጥያቄዬን በማያያዝ፣ " ... ክቡር ጄኔራል ከጦር ሚኒስትርነት በኋላ ፓሪስ አምባሳደር ሆነው የተላኩት፣ ከጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ጋር ባላችሁ መቀራረብና ወዳጅነት ምክንያት ነው እየተባለ በአዲስ አበባ የሚነፍስ ወሬ አለ። ስለዚህ ጉዳይ ያለዎትን አስተያየት ቢነግሩኝ ለሞያዬ ይረዳኛል ... "

መልስ፣ ጥያቄህን ግልጽ አድርገህ አላቀረብከውም። ... አዲስ አበባ የተወራው አቢይ አበበ የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ፓርቲ ስለሆነ፣ በግዞት ፓሪስ ተልኳል ተብሎ ነው። አንተም የምትፈልገው በዚህ ጉዳይ የእኔን ስሜት ለማወቅ ነው። እኔም የምነግርህ ከልቤ የማምንበትን እውነተኛውን ጉዳይ ነው። እኔ ፓሪስ መምጣቴን እንደ ግዞት አድርጌ አልተመለከትኩትም። ይልቁንም በጣም ደስ ብሎኛል። እርግጥ ነው! ከጸሐፊ ትዕዛዝ ሸረት በኋላ እኔ የጃንሆይ ሚኒስትር ሆኜ እንድቆይ ስላልተፈለገ፣ ከመንግሥት መምሪያ አደባባይ ዘወር እንድል ታስቦ ፓሪስ መጥቻለሁ። ይሁን እንጂ ጃንሆይ ጥሩ ዕድል ሰጥተውኛል ብዬ ከማመስገን በስተቀር፣ ምንም ዓይነት ቅሬታ የለኝም። የእኔና የጸሐፊ ትዕዛዝ ወዳጅነት ግን ሰው እንደሚያወራው በፖለቲካ ፓርቲ ዓይነት አይደለም። የወዳጅነታችን መሠረቱ በግል የመግባባትና የመጣጣም ጉዳይ ነው። ይህም ወዳጅነት፣ ትናንት እንደነበረው ዛሬም አለ። ነገም አይለወጥም።

ከዚህ በላይ እንደተነበበው፣ በጨዋነታቸውና በመልካም ምግባራቸው የታወቁት ጄኔራል አቢይ አበበ፣ በወልደጊዮርጊስ ሸረት ምክንያት ከቤተመንግሥቱ አደባባይ ዘወር እንዲሉ መደረጋቸውን እንጂ፣ በግዞት ፓሪስ አለመላካቸውን የሚያምኑበትን ትክክለኛውን ጉዳይ በግልጽ አስረድተዋል።

2. የትምህርትና የሥነ ጥበብ ሚኒስቴርን ከንጉሠ ነገሥቱ ቀጥሎ <u>ለዘጠኝ ዓመታት በምክትል ሚኒስትርነት ሲመሩ የቆዩት አቶ አካለወርቅ ሀብተወልድ፣</u> ስሙ ለመጀመሪያ ጊዜ ለሕዝብ የተገለጸው የሕዝባዊ ኑሮ ዕድገት ሚኒስቴር ምክትል ሚኒስትር ተብለው ተሾሙ። አቶ አካለወርቅ የካቢኔ አባል ሆነው፣ ለብዙ ዓመታት የትምህርት ሚኒስቴርን በምክትል ሚኒስትርነት ደረጃ ሲመሩ የቆዩት፣ ሚኒስትሩ ራሳቸው ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በመሆናቸው ስለሆነ፣ ወደ ሌላ ሚኒስቴር ሲዛወሩ የሚኒስትርነት ደረጃ እንደሚሰጣቸው የሚጠበቅ ነበር። ከዚህ በላይ ደግሞ ይህ "የሕዝባዊ ኑሮ ዕድገት" የተባለው ሚኒስቴር ዓላማውና ግብሩ ምን መሆኑ ተገልጾ አዋጅ ያልወጣለት ሲሆን፣ ቢሮም ሠራተኛም የሌለውና በጀትም ያልተመደበለት ነው። እርግጥ ነው! ከሦስት ዓመታት በፊት ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና አቶ መኰንን ሀብተወልድ በዚያን ጊዜ የፕላኒንግ ቦርድ ፕሬዚዳንት ከነበሩት ከአቶ ይልማ ዴሬሣ ጋር ሆነው፣



ክቡር ራስ አበበ አረጋይ
በሌፍትናንት ጄኔራል ወታደራዊ ማዕረግ በአዲስ መልክ የተቋቋመው
የመከላከያ ሚኒስትር ሆነው ተሾሙ።

በቅርቡ በሕንድ አገር ተቋቁሞ ጥሩ ውጤት የሰጠውን "የሕዝባዊ ኑሮ ዕድገት ማስፋፊያ" የተባለውን ሚኒስቴር በኢትዮጵያ ለማቋቋም ጥናት እንዲደረግ ተስማምተውበት ነበር። ነገር ግን ጥናቱም ሳይጠናቀቅ፣ ለሚኒስቴሩም መቋቋም አዋጅ ሳይወጣ ከቆየ በኋላ፣ ከወልደጊዮርጊስ የሥልጣን መነሳት ማግሥት አቶ አካለወርቅ በዚህ በሐሳብ ላይ ለተፀነሰ ሚኒስቴር ምክትል ሚኒስትር ሲባሉ፣ ከነበሩት ቦታ ጋር ሲመዛዘን ሽረት እንጂ ሹመት ሊባል አለመቻሉ በማንም ዘንድ ግልጽ ሆኖ ታየ። ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የማንንም ሐሳብ ሳይጠይቁ በቅርብ አገልጋያቸው ሆነው ሲሠሩ በቆዩት በአካለወርቅ ላይ የወሰዱት እርምጃ በምን ምክንያት ይሆን ለሚለው ጥያቄ ሦስት ዓይነት አስተያየቶች ሲሰነዘሩ ተሰምቷል።

1. ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ከመሻራቸው ከጥቂት ቀናት በፊት በሥራ ምክንያት አቶ አካለወርቅ ከጃንሆይ ጋር ግጭት ደርሶባቸው ስለነበረ፣ ከዚህ ቂም የተነሣ ንጉሠ ነገሥቱ ለመቅጣት ስለፈለጉ ነው ተብሏል።

2. አካለወርቅ ሀብተወልድ ጸሐፊ ትዕዛዝ በተሻሩበት ዕለት፣ ከሰዎች ጋር በተለይም ከትምህርት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር ከአቶ በለጠ ገብረጻድቅ ጋር ሐሳብ ሲለዋወጡ፣ "በጽሕፈት ሚኒስትራቸው ላይ ጃንሆይ የወሰዱት እርምጃ በትክክለኛ ፍርድ ላይ የተመሠረተ አይደለም" የሚል ትችት መስጠታቸው ስለተሰማ ነው ይባላል።

3. ጃንሆይ ወልደጊዮርጊስን ከሻሩ በኋላ፣ ከሀብተወልድ ወንድማማቾችም መካከል በሹመት የሚያገለሉት ሰው መኖሩን ለማሳየት ስለፈለጉ፣ ነው እየተባለ ተወርቷል።

ከእነዚህ ከሦስቱ አስተያየቶች ደራሲው ምርምር አድርጐ የተቀበለው፣ በሁለተኛውና በሦስተኛው ተራ ቁጥሮች ላይ የተነገሩትን ነው። ወደ ኋላ መለስ ብለን ስንመለከተው፣ ገና ከመጀመሪያው ስለ ጸሐፊ ትዕዛዝ ጉዳይ የዘውድ ምክር ቤቱ እየተሰበሰበ በሚመክርበት ጊዜ፣ ለጃንሆይ ጠቃሚ የሚሆነው ወልደጊዮርጊስንና መኰንን ሀብተወልድን ከየሥልጣናቸው አብሮ ማሰናበት ነው እንጂ፣ አንዱን ከሌላው መርጦ ማቆየት አያስፈልግም። ሁለቱም ሰዎች በመሳፍንትና በመኳንንት ላይ ያላቸው የግል ጥላቻ የተደበቀ ምሥጢር አይደለም የሚል ትችት ተሰጥቶ እንደነበረ ይታወሳል።* ይሁን እንጂ፣ ንጉሠ ነገሥቱ ይህን ሐሳብ አልተቀበሉም። ያው እንደታየው ወልደጊዮርጊስን አሰናብተው፣ መኰንን ሀብተወልድን በገንዘብ ሚኒስትርነታቸው እንዲቀጥሉ አድርገዋል።

ወልደጊዮርጊስን ሽረው፣ ሦስቱንም ሀብተወልድ ወንድማማቾች በካቢኔ ሚኒስትርነታቸው አቆዩዋቸው ከሚል ትችት ለመዳን፣ ንጉሠ ነገሥቱ ከሦስቱ አንዱን ዘወር ማድረግ አለብኝ ብለው ማንንም ሳያማክሩ የራሳቸውን ውሳኔ አደረጉ። ለዚህም ቀደም ሲል እንደተገለጸው፣ አካለወርቅን ከትምህርት ሚኒስቴር አንስተው ገና ላልተፈጠረ ሚኒስቴር ምክትል ሚኒስትር በማድረግ ያለ ቢሮና ያለ ሥራ አስረው አስቀመጧቸው። ይህንንም ሲያደርጉ፣ የትምህርት ም/ሚኒስትሩ በጸሐፊ ትዕዛዝ ላይ የተደረገው ሽረት ትክክለኛ ፍርድ አይደለም ሲሉ አስተያየታቸውን ሰጥተዋል የሚል መረጃ ከገነተ ልዑል ቤተመንግሥት ደርሶ

---

* ገጽ 561 ላይ ተመልከት

ስለነበረ፤ ጃንሆይ በአቶ አካለወርቅ ላይ ለወሰዱት እርምጃ ተጨማሪ ምክንያት እንደሆናቸው ብዙ ሰዎች አምነውበታል።

አቶ አካለወርቅም በእነዚህ ምክንያቶች ሁሉ ከደረሰባቸው ብስጭት የተነሳ፤ ብዙ ታመው ለአንድ ዓመት ያህል ሲቸገሩ ከቆዩ በኋላ፤ ንጉሠ ነገሥቱ ማንም ሳያስታውሳቸው ራሳቸው አስበው፤ የሕዝብ ጤና ጥበቃ ሚኒስትር አድርገው ሾሟቸው። እንግዲህ! ከዚህ በላይ እንደተገለጸው አቶ አካለወርቅ በጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ጉዳይ ከተጠቂዎቹ እንጂ ከተጠቃሚዎቹ ወገን እንዳልነበሩ መገንዘብ ይቻላል።

3. ለብዙ ዓመታት የሸዋ ጠቅላይ ግዛት እንደራሴ የነበሩት ፊታውራሪ ጸሐዩ እንቁሥላሴ የወልደጊዮርጊስ ልዩ ወዳጅ ናቸው በመባል፤ ለጥቂት ጊዜ የጤና ጥበቃ ም/ሚኒስትር ከሆኑ በኋላ፤ የገሙጎፋ ጠቅላይ ግዛት እንደራሴ ተብለው ወደ ጨንቻ ተላኩ። ፊታውራሪ ጸሐዩ (ኋላ ደጃዝማች) ከጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ጋር ያላቸውን ጽኑ ወዳጅነት እስከ ሕይወታቸው ፍጻሜ ድረስ የጠበቁ ናቸው።

4. ኮሎኔል ክፍሌ ዕርገቱ (ኋላ ደጃዝማች) የሕዝብ ፀጥታ ጥበቃ ምክትል ሚኒስትር ሆነው ከጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ጋር ወዳጅነት እንዳላቸው የታወቀ ነበር። ይሁን እንጂ በፀጥታው አጠባበቅ ጉዳይ ለንጉሠ ነገሥቱ በታማኝነት ከመሥራት በስተቀር በጸሐፊ ትዕዛዝ ወዳጆችና ተቃዋሚዎች መካከል የተጫወቱት ሚና አልነበረም። ሆኖም ከጸሐፊ ትዕዛዝ ሽረት በኋላ በነበሩበት ቦታ ማቆየቱ አይገባም ተብሎ፤ የሐረር ጠቅላይ ግዛት የልዑል መኰንን መሥፍነ ሐረር እንደራሴ ሆነው እንዲሾሙና፤ በምትካቸው ጃንሆይ በጣም የሚወዷቸው በተጨማሪም ዘመዳቸው የሆኑት ብሪጋድየር ጄኔራል መርዕድ መንገሻ የፀጥታ ም/ሚኒስትር ተብለው ተሾሙ። ስለዚህ፤ የኮሎኔል ክፍሌ ዕርገቱ ጉዳይ እንደ ጄኔራል አቢይ የሥራ ዝውውር እንጂ ሽረት ወይም ግዞት ደርሶባቸዋል ማለት አይቻልም።

5. ኮሎኔል ታምራት ይገዙ የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ የፍርድ ም/ሚኒስትር ሆነው በመልካም ግንኙነት የሠሩ ናቸው። ሆኖም ከለውጡ በኋላ በነበሩበት ቦታ ላይ ማቆየቱ አዲስ ለተሾሙት የፍርድ ሚኒስትር ተስማሚ አይሆኑም ተብሎ የደጃዝማች መሥፍን ስለሺ ቦታ የነበረውን የከፋ ጠቅላይ ግዛት እንደራሴ ሆነው ተሾሙ። ኮሎኔል ታምራት በዚያን ጊዜ ምንም እንኳ ከጸሐፊ ትዕዛዝ ጋር በወዳጅነት ቅርበት አላቸው እየተባለ ቢወራም፤ በሽረት እንዲቀጡ አልተፈለገም። እንዲያውም የጠቅላይ ግዛት እንደራሴ ሲሆኑ ደረጃቸውና ቀለባቸው እንደሚኒስትሮች ስለሆነ፤ ከዕድገት ጋር የሥራ ዝውውር ከመደረጉ በስተቀር ሌላ የደረሰባቸው ነገር የለም።

6. አቶ በለጠ ገብረጻድቅ፤ ከትምህርት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተርነት ተነስተው በሲዳሞ ጠቅላይ ግዛት የጀምጀም አውራጃ ገዥ ተብለው ተሾሙ። ይህም ሽረት የደረሰባቸው ከጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ጋር ልዩ የሆነ የወዳጅነት ግንኙነት አላቸው በመባል ነው።

አቶ በለጠ ገብረጻድቅ የትምህርት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር በነበሩበት ጊዜ፤ ከአለቃቸው ከአቶ አካለወርቅ ጋር በጣም የሚግባቡና በአሠራር የሚጣጣሙ ነበሩ። ከዚህም የተነሳ፤ አቶ በለጠ በዋና ዲሬክተርነት የያዙት ሥልጣን ከሚኒስትሩ ያነሰ

አልነበረም። ከጀምጀም ግዛት ተነስተው የባሕር ዳር አውራጃ ገዥ ከሆኑ በኋላ፣ አዲስ አበባ ሲመለሱ፣ የዚህ መጽሐፍ ደራሲ ከጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ጋር ስለነበራቸው ወዳጅነት ጉዳይ ሲያነጋግራቸው፣ አስተያየታቸውን እንደሚከተለው ሰጥተውታል። " ... **እኔ በለጠ ገብረጻድቅ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን ያወቅኳቸው፣ የሐረር ጠቅላይ ግዛት ዋና ጸሐፊ ከነበርኩበት ሥራ አዲስ አበባ አስመጥተው የአገር ግዛት የአስተዳደር ዲሬክተር አድርገው ከሾሙኝ በኋላ ነው። እንደማስታውሰው እንደ ኢት.አቆ በሐምሌ 1938 ዓ.ም ይመስለኛል።** ጸሐፊ ትዕዛዝ የአገር ግዛት ሚኒስትር ሆነው እስከቆዩበት ጊዜ ድረስ፣ ለሦስት ዓመታት ያህል አብሬያቸው ከሠራሁ በኋላ፣ በአቶ አካለወርቅ ሀብተወልድ ም/ሚኒስትርነት (ሚኒስትሩ ጃንሆይ ሆነው) ለሚመራው የትምህርትና የሥነ ጥበብ ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር ሆኜ ተሾምኩ። ከአቶ አካለወርቅ ጋር እንድሠራ የመረጡኝ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ መሆናቸውን አውቃለሁ። ሹመቱ በተሰጠኝ ዕለት " ... **አይዞህ በለጠ! አካለወርቅና አንተ ብርቱ ሠራተኞች መሆናችሁን ስለማውቅ፣ በፍጹም መግባባትና መተባበር እንደምትሠሩ እርግጠኛ ነኝ** ... " አሉኝ። እውነትም ጸሐፊ ትዕዛዝ እንዳሉት፣ ከአቶ አካለወርቅ ጋር በትምህርት ሚኒስቴር ለዘጠኝ ዓመታት አብረን በሠራንበት ዘመን፣ በመካከላችን ፍጹም የሆነ መተማመንና መግባባት ስለነበረ፣ አንድም ቀን የሥራ ግጭት ተፈጥሮብን አያውቅም። የትምህርት ሚኒስትሩ ጃንሆይ በመሆናቸው፣ ከሌሎቹ ሚኒስቴሮች ሁሉ ጉዳዮቻችንን በፍጥነት ለማስፈጸም የሚያስችል ዕድል ነበረን። ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስም ዋና ደጋፊያችንና ረዳታችን ነበሩ። እኛን የሚያስቸግሩን የገንዘብ ሚኒስትሩ አቶ መኰንን ሀብተወልድ ናቸው። እሳቸውም ትምህርት ሚኒስቴርን ለመጉዳት ሳይሆን፣ ሕጉን በመከተል ያለፈውን ወር የወጭ ሂሣባችሁን ሳታወራርዱ፣ ለሚቀጥለው ወር ወጭ በቅድሚያ ገንዘብ መጠየቅ አትችሉም በማለት ነበር። ለዚህም አቶ አካለወርቅ ከወንድማቸው ከአቶ መኰንን ሀብተወልድ ጋር መሟገቱን እየፈሩ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን አማላጅ በመላክ ጉዳያችንን እንደ ጥያቄያችን ያስፈጽሙልን ነበር። እንግዲህ፣ አለቃዬ አቶ አካለወርቅና እኔ ከጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ጋር የተለየ የወዳጅነት ግንኙነት አላቸው ተብለን አንዳንድ እርምጃዎች የተወሰዱብን በትክክለኛ አስተያየት አይደለም። እኔ እስከማውቀው፣ አቶ አካለወርቅና እኔ ጸሐፊ ትዕዛዝን የምናከብራቸውና የምናደንቃቸው፣ በአሠራራቸውና በአመራር ውሳኔያቸው ነው እንጂ፣ በፖለቲካ ዕቅዳቸውና ከጃንሆይ ጋር ላላቸው ግንኙነት አማካሪዎቻቸው ወይም ረዳቶቻቸው ሆነን አይደለም። በተለይ እኔ በግል ወዳጅነት እቤታቸው ገቢና ወጭ አልነበርኩም። በሥራም ጉዳይ ለብቻዬ ጠርተው የሚያነጋግሩኝ፣ አቶ አካለወርቅ በሌሉበት ጊዜ የትምህርት ሚኒስቴር ተጠባባቂ ስሆን ብቻ ነው እንጂ፣ ከዚያ ውጭ አልነበረም።

... ጸሐፊ ትዕዛዝ በተሻሩ ዕለት (ሚያዝያ 17/1947) አቶ አካለወርቅ አንድ ስሙን መግለጽ የማልፈልገው ሀብታም ነጋዴ ለትምህርት ሚኒስቴር መሠረተ ትምህርት ማስፋፊያ በየዓመቱ እርዳታ ስለሚሰጥ፣ ይህን ሰው በቢሮአቸው ተቀብለው ሲያነጋግሩ፣ እኔም እንድካፈል ጠርተውኝ ተገኝቼ ነበር። ከእርዳታ ሰጭያችን ጋር በምንነጋገርበት ሰዓት፣ ስልክ ተደውሎ የጸሐፊ ትዕዛዝ ወደ አሩሲ መዛወር ለአቶ አካለወርቅ ተነገራቸው። ይህን ዜና ስንሰማ ሁላችንም የማንጠብቀው ጉዳይ ስለሆነ፣ በጣም ደነገጥን። ነጋዴው ወዳጃችንም ከአቶ አካለወርቅና ከእኔ ጋር ሆኖ ወየጉድ? እያለ ስሜታችንን ማጀብ ጀመረ። አቶ አካለወርቅም በጸሐፊ ትዕዛዝ ላይ በደረሰው ሁኔታ አዝነው፣ " ... **ጃንሆይ የጽሕፈት ሚኒስትራቸውን ካስፈለገ ወደ ሌላ ሚኒስቴር ማዛወር ነበር እንጂ፣ እስከዚህ ድረስ እርቆ መጣል ትክክለኛ ፍርድ አይደለም** ... " የሚል አስተያየት



ክቡር ደጃዝማች መስፍን ስለሺ (ኋላ ራስ) የአገር ግዛት ሚኒስትር ሆነው ተሾሙ፤ ክቡርነታቸው በአምስቱ ዓመታት ውስጥ ለነፃነት የተዋጉ የታወቁ ስመጥር አርበኛ ሲሆኑ፤ እስከመጨረሻው የንጉሠ ነገሥቱ ታማኝና ዋና ባለሟል ነበሩ። በወልደጊዮርጊስም ጉዳይ በግርማዊት ቪላ በተደረጉት ታላላቅ ስብሰባዎች ከቅርበታቸው የተነሳ ተካፋይ ሆነዋል።

ሰጡ። በዚህ ጊዜ የእኔም ዕምነት እንደዚሁ መሆኑን ስገልጽ፤ ነጋዴው ወዳጃችንም ከእኛው ጋር ተስማሚ ሆነ።

በማግሥቱ ይኸ ነጋዴው ወዳጃችን ለካስ የፀጥታ ሥራ ተከታታይ ኖሮ፤ " ... አካወርቅና በለጠ በጸሐፊ ትዕዛዝ ሽረት የጃንሆይን ውሳኔ በመቃወም ሲያለቅሱ በዓይኔ አይቻለሁ ... " የሚል ሪፖርት ማቅረቡን የግቢ ሰዎች ነገሩን። ጃንሆይ ይህንን ሲሰሙ በአቶ አካለወርቅ ላይ በጣም መቆጣታቸው የታወቀ ነበር። ሆኖም ለምን እንዲህ አልክ? ብለው አልጠየቋቸውም። ወዲያው የትምህርት ሚኒስቴርን አቶ ከበደ ሚካኤል በዋና ዲሬክተርነት እንዲመራው አድርገው፤ አቶ አካለወርቅን የሚገባቸውን የሚኒስትርነት ደረጃ በመንፈግ፤ ምንም ሥራ ወደሌለበት ወደ አልታወቀ ሚኒስቴር ምክትል ሚኒስትር ብለው ባዶ ወንበር ላይ አስቀመጧቸው። እኔም ከአቶ አካለወርቅ ቀጥሎ ወደ ጀምጀም ተልኬ አዲሱ ሥራዬን ተረከብኩ።

<u>አቶ አልፍሬድ ሻፊ፤</u> ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ የአገር ግዛት ሚኒስትር ከነበሩበት ጊዜ ጀምሮ (1935-1941) ለሕዝብ ፀጥታ ጥበቃ መሥሪያ ቤት መጀመሪያ በዲሬክተርነት፤ ኋላ በዋና ዲሬክተርነት ለብዙ ዓመታት የሠሩ ናቸው። አቶ አልፍሬድ ፈረንሣዊኛ የሚያውቁ፤ የዘመኑን ሥልጣኔ ሕይወት የሚከተሉ ብልህና ጠንካራ ሠራተኛ ነበሩ። ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስም የአቶ አልፍሬድን ንቃትና የሥራ ችሎታ በማድነቅ ያቀርቧቸው ነበር።

እንደ ኢ.ት.አቆ በሚያዝያ 1947 ዓ.ም ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ከሥልጣን ሲነሱ፤ አቶ አልፍሬድ ሻፊ የእሳቸው ወገን ናቸው ተብለው ስለተቆጠሩ፤ ከነበራቸው የዋና ዲሬክተርነት ደረጃ ተቀንሰባቸው፤ መጀመሪያ ለወለጋ ጠቅላይ ግዛት፤ ወዲያው ደግሞ ከዚያ ተነስተው ለገሙጎፋ ጠቅላይ ግዛት የአስተዳደር ዲሬክተር ተብለው ወደ ጨንቻ (በዚያን ጊዜ የጠ/ግዛቱ ዋና ከተማ) ተላኩ። የዚህ መጽሐፍ ደራሲ ስለ አቶ አልፍሬድ ሻፊ ሽረትና ዝውውር እንደተከታተለው፤ የተወሰደባቸው እርምጃ ሁሉ ትክክል እንዳልሆነ ለመረዳት ችሏል። ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስም ቀደም ሲል እንደተገለጸው፤ አልፍሬድን የወደዷቸው በሥራ ችሎታቸውና ባላቸው ትጋት እንጂ በተለየ የግል ወዳጅነት አልነበረም።



ከንጉሠ ነገሥቱ ቀጥሎ ለዘጠኝ ዓመታት የትምህርት ሚኒስቴርን ሲመሩ የቆዩት አቶ አካለወርቅ ሀብተወልድ፣ ከወልደጊዮርጊስ በኋላ በተደረጉት ሹመቶች፣ ጉዳት ከደረሰባቸው ሰዎች መካከል አንዱ ናቸው።

" ... ጃንሆይ የጽሕፈት ሚኒስትራቸውን ካስፈለገ ወደ ሌላ ሚኒስቴር ማዛወር ነበር እንጂ፣ እስከዚህ ድረስ አርቆ መጣል ትክክለኛ ፍርድ አይደለም ... "

አወ.ሀ 17/8/47

# ምዕራፍ ፲፫

## ስለ ጸ.ት ወልደጊዮርጊስ ሥልጣንና ሽረት

### ከጠቅላይ ሚኒስትር አክሊሉ ጋር

በርዕሱ በተጠቀሰው ጉዳይ፣ በምን ምክንያትና በምን አጋጣሚ፣ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ጠቅላይ ሚኒስትር የነበሩትን ጸሐፊ ትዕዛዝ አክሊሉ ሀብተወልድን ኢንተርቪዩ አድርጌ ሰፊ የሆነ አስተያየት ለመጻፍ እንደቻልኩ፣ ለአንባቢዎቼ ለማስረዳት እወዳለሁ።

እንደ ኢ.ት. አቆ. በ1962 ዓ.ም ክቡር ደጃዝማች ከበደ ተሰማ የታሪክ ማስታወሻቸውን ጽፈው ሲያቀርቡ፣ ብዙ ሕዝብ ምን ያህል እንደተደሰተና ጸሐፊውን ምን ያህል እንደአደነቃቸው ይታወሳል። ከንግሥተ ነገሥታት ዘውዲቱ ምኒልክ ጀምሮ እስከ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ዘመነ መንግሥት ድረስ የተጻፈውን የከበደ ተሰማን የታሪክ ማስታወሻ ካነበብን በኋላ፣ ወዳጄ ወንድሜ አቶ አሰፋ ድፋዬና እኔ፣ ጠቅላይ ሚኒስትር ጸሐፊ ትዕዛዝ አክሊሉ ሀብተወልድ፣ ስለ ኢትዮጵያ የውጭ ጉዳይ ፖሊሲና ስለ ኤርትራ ጉዳይ የታሪክ ማስታወሻቸውን እንዲጽፉ ለማሳሰብ፣ ቀጠሮ እንዲሰጡን ጠየቅናቸው። በዚያን ጊዜ፣ አቶ አሰፋ ድፋዬ የአዋሽ ሸለቆ ባለሥልጣን ም/ሚኒስትር ሲሆን፣ እኔ ደግሞ ከማስታወቂያ ሚኒስቴር ረዳት ሚኒስትርነት በፓሪስ የኢትዮጵያ ኤምባሲ ሚኒስትር ካውንስለርነት ተሾሜ ለጉዞው በመዘጋጀት ላይ ነበርኩ።

እንደ ኢ.ት. አቆ. መስከረም 2 ቀን 1963 ዓ.ም ከምሽቱ በ1 ሰዓት ጸሐፊ ትዕዛዝ አክሊሉ በመኖሪያ ቤታቸው ከተቀበሉን በኋላ፣ ጉዳያችሁ ምን ነበር? ብለው ሲጠይቁን፣ አቶ አሰፋ ድፋዬ የሚከተለውን ተናገረ።

"ጌታዬ እንደሚያውቁት ይህች ያለንባት ጊዜያዊ ዓለም እስከ መቼ እንደምታኖረንና መቼ እንደምታሰናብተን ለማናችንም ለትልልቆቹም ሆነ ለትንንሾቹ አትናገርም። እንዲሁ በደፈናው ዛሬ አለን የነገውን አናውቅም እያልን፣ እስከምንጠራ ድረስ ከመጠበቅ በስተቀር ሌላ ምርጫ የለንም። የቀድሞዎቹ አባቶቻችን በሕይወት ባሉበት ዘመን፣ በመጀመሪያ ለልጆቻቸው ምን ትተውላቸው ለመሄድ እንደሚችሉ ሲጨነቁና ሲያስቡበት ይታዩ ነበር። ከእነሱም የቀጠለው ትውልድ ምንም እንኳ ዘመናዊ ሥልጣኔ የፈነጠቀበትን ሕይወት የቀመሰ ቢሆንም፣ አስተሳሰቡ ከቀድሞዎቹ የተለየ አይደለም። በሠለጠነው ዓለም ያሉት ሕዝቦች ግን፣ የሕይወት ዘመናቸውን ከመፈጸማቸው በፊት፣ ለልጆቻቸውና ለቤተሰቦቻቸው ትተው የሚሄዱትን ማሰባቸው የማይቀር ቢሆንም፣ በይበልጥ የሚደክሙትና ብዙ ጥረት የሚያደርጉት፣ ለአገር ጠቃሚ የሚሆን የታሪክ ቅርስ ትተን መሄድ አለብን በማለት ነው። ስለዚህም፣ ራሳቸው የተካፈሉበትንም ሆነ በዘመናቸው ደርሶ ያዩትን ታሪክ እየጻፉ ለትውልድ በማስተላለፋቸው፣ ስማቸው ከመቃብር በላይ ሆኖ ሲነገርላቸው ይኖራል። ይኸ መቸም በአገራችን እስከ ዛሬ ያልተለመደ ሆኖ የኖረ ነበር። ዛሬ ግን የደጃዝማች ከበደ ተሰማ የታሪክ ማስታወሻ ተዘጋጅቶ በመቅረቡ፣ የብዙውን ሕዝብ ሕሊና ቀስቅሶታል። እንደ ከበደ ተሰማ

ሌሎቹም ኢትዮጵያን በከፍተኛ ደረጃ ያገለገሉና ዛሬም በማገልገል ላይ የሚገኙት ታላላቅ ሰዎች፣ የታሪክ ማስታወሻቸውን እያዘጋጁ እንዲተውልን ጃንሆይ ትዕዛዝ እንዲሰጧቸው እናመለክት፣ እስከማለት የደረሱ ሰዎች አሉ፡፡

በዚህ ጉዳይ ከወንድሜ ከዘውዴ ረታ ጋር ስንወያይ፣ በመጀመሪያ የታየን የእርስዎ ታሪክ ነው፡፡ ኢትዮጵያን ማገልገል የጀመሩት፣ በዚያ ነፃነታችን በፋሽስት በተያዘበት በመከራው ዘመን ነው፡፡ ከዚያም ወደ አገርዎ ተመልሰው፣ የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴርን በመሩበት በአሥራ ስድስት ዓመታት ውስጥ፣ ከውጭ አገሮች ጠላቶቻችን ጋር ያደረጓቸው የፖለቲካና የዲፕሎማሲ ጦርነቶች ብዙዎች ናቸው፡፡ ስለዚህ፣

1ኛ/ ከነፃነታችን መመለስ በኋላ ሲካሄድ ስለቆየው የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መንግሥት የውጭ ፖሊሲ፣

2ኛ/ ኤርትራን ወደ እናት አገሯ ወደ ኢትዮጵያ ለመመለስ በኢንተርናሽናል የፍርድ ሸንጐዎች ላይ ስለተደረገው ሙግት፣

ጌታዬ የታሪክ ማስታወሻዎን ጽፈው ለኢትዮጵያ ሕዝብ እንዲያበረክቱ በብርቱ ለማሳሰብ ሁለታችንም ወደ እርስዎ መጥተናል፡፡ ዘውዴና እኔ ወደ ጌታዬ ዘንድ ከመምጣታችን በፊት፣ በእነዚህ በሁለቱ ዋና ዋና ጉዳዮች ላይ ከተስማማን በኋላ ከእነዚሁ ጋር የሚጨመር አንድ ዋና ጉዳይ አለ ብሎ አቶ ዘውዴ ሐሳቡን ማቅረብ ስለሚፈልግ፣ እሱ ራሱ ለጌታዬ እንዲገልጽ ፈቃድዎን እጠይቃለሁ" በማለት ንግግሩን ሲፈጽም፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ያንተ ተጨማሪው ሐሳብ ምንድን ነው? ብለው ጠየቁኝ፡፡

" ... ከወንድሜ ከአቶ አሰፋ ድፋዬ ጋር ጌታዬ ስለሚያዘጋጁት የታሪክ ማስታወሻዎች ስናጠና፣ ከእነዚህ ከተጠቀሱት ከሁለቱ ዋና ዋና ጉዳዮች ሌላ፣ በበኩሌ አንድ ተጨማሪ ታሪክ እንዲጻፍ ያሳሰብኩት፣ የኢትዮጵያ ሕዝብ እውነተኛውን ጉዳይ ለማወቅ እጅግ የሚጓጓውን የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን የሥልጣን ኃይልና በመጨረሻውም የደረሰባቸውን ሽረት ነው፡፡ በዚህ ጉዳይ እስከ ዛሬ ድረስ፣ በአፍ ታሪክ የሚነዛውንና የሚነገረውን ስንመለከት፣ ሐቁን እየሸፈነና መሠረቱን እየለቀቀ፣ የደጋፊዎችና የተቃዋሚዎች የፈጠራ አስተያየት ስለበዛበት፣ የዛሬውና በተለይም መጭው ትውልድ እውነተኛው ታሪክ ምን እንደነበረ ለመረዳት ጨርሶ ከማይችልበት ደረጃ ላይ ይወድቃል ብዬ እሠጋለሁ፡፡ ስለዚህ ጌታዬ የሚያዘጋጁት የታሪክ ማስታወሻ፣ የኢትዮጵያን የውጭ ጉዳይ እንቅስቃሴ በሚመለከት ብቻ የተወሰነ እንዳይሆን፣ በአገር ውስጥም ደርሶ የታየው የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና የአቶ መኰንን ሀብተወልድ የሥልጣን ትብብር፣ በምን አኳኋን ሲራመድ እንደቆየና፣ በመጨረሻው ጃንሆይ ጸሐፊ ትዕዛዝን ለመሻር የወሰዱት እርምጃ በምን ምክንያት እንደሆነ ለሕዝቡ ቢገለጽለት፣ የአፍ ታሪክንና የልብ ወለድን ፈጠራ ከማግበስበስ እንደሚድን ከልብ አምናለሁ" ብዬ ሐሳቤን ገለጽኩላቸው፡፡ ጸሐፊ ትዕዛዝ እኔ ከተናገርኩ በኋላ፣ ወደ አቶ አሰፋ ዞወር ብለው፣ በዚህ ዘውዴ ባቀረበው ሐሳብ ላይ ያንተ አስተያየት ምንድን ነው? ሲሉ ጠየቁት፡፡

" .... እኔ የዘውዴን ሐሳብ ሳላመነታ እደግፋለሁ፡፡ የምደግፈውም የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ጉዳይ በታሪክነቱ ሊጻፍ የሚገባው መሆኑን ነው፡፡ ነገር ግን ጌታዬ ከሚያዘጋጁት ታሪክ ጋር ተያይዞ እንዲጻፍ የተባለውን ሐሳብ አልደግፍም፡፡

ከዘውዴ ጋር የተለያየነው በዚህ ብቻ ነው። በእኔ አስተያየት የጸሐፊ ትዕዛዝን ታሪክ፣ እንደ ተክለጻድቅ መኩሪያ የመሰለ ደራሲ፣ ወይም ደግሞ እንደ እሱ እንደ ዘውዴ ረታ የመሰለ ጋዜጠኛ ቢጽፈው የተገባ ይመስለኛል ... " ሲል አስተያየቱን ገለጸ። ጸሐፊ ትዕዛዝ አክሊሉ የሁለታችንንም ሐሳብ ካዳመጡን በኋላ፣ የሚከተለውን መልስ ሰጡን።

1. እኔ የራሴን የታሪክ ማስታወሻ (ሜሚር) እንድጽፍ ያሳሰባችሁኝን ያዳመጥኩት በደስታ ነው። እኔም ምቹ ጊዜ የሚኖረኝ መቼ እንደሆነ ባላውቀውም፣ ስለ ኢትዮጵያ የውጭ ፖለቲካ አመራርና ስለ ኤርትራ ጉዳይ በሥራው የተካፈልኩበትን ለመጻፍ ከልቤ እመኛለሁ። ይህም ምኞት፣ ምኞት ሆኖ እንዳይቀር በቶሎ ሥራውን መጀመር አለብኝ። ዘውዴ፣ አዲሱ ሥራህን ፓሪስ በምትጀምርበት ጊዜ*፣ ድሮ "Agence Havas" አሁን "Agence France Presse" በተባለው ድርጅት፣ የታወቀ ጋዜጠኛ "Rene Benezra" የሚባል ወዳጅ ስላለኝ፣ ፈልገህ ታገናኘኛለህ። እኔ የምጽፈውን "ሜሚር" ለዝግጅቱም ሆነ ለሕትመቱ ለመርዳት ሙሉ ፈቃደኛ መሆኑን ደጋግሞ ነግሮኝ ነበር። እንግዲህ፣ የፈጀውን ጊዜ ቢፈጅም፣ ሥራውን በቶሉ እጀምራለሁ።

2. አስፋ ድፋዬ እንደተናገርከው፣ የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን ሥልጣንና ሽረት፣ እኔ ሳልሆን ሌላ ሰው ቢጽፈው ይሻላል። እንዲያውም ዘውዴ ረታ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ በተሻሩበት ዕለት በቤተ መንግሥቱ የነበረውን ግርግር፣ በአረንጓዴው ሳሎን የተደረገውን የሹመት አፈጻጸም በጋዜጠኝነቱ አይቻለሁ በማለት፣ ከዚህ ቀደም አሚሙቀህ ስትናገር ሰምቼሀለሁ። ስለዚህ ፍላጐቱና ዝንባሌው ስላለህ፣ የበሰለ ምርምር አድርገህ አንተው ብትጽፈው ጥሩ ነው። እኔ እንደሚመስለኝ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ የመጻፍ ችሎታቸው ከፍ ያለ ስለሆነ፣ የራሳቸውን ታሪክ እስካሁን ሳያዘጋጁት አልቀሩም። ዘውዴ ግን፣ በጋዜጠኝነት ሞያህ በጉዳዩ ላይ ከምታደርገው ምርምር ሌላ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን ኢንተርቪዩ ጠይቀህ፣ ለማንም ወገን ሳታዘነብል እውነተኛውን ታሪክ ልታዘጋጅ ትችላለህ። እኔም የማውቀውንና የሚመስለኝን ሁሉ እነግርሃለሁ። ለምሳሌ፣ አቶ መኩሪያን ከጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ጋር አለመግባባት የደረሰበትን ሁኔታ ለእኔና ለወንድሞቼ "እንድታውቁት" በሚል የሰጠን ማስታወሻ አለ። እሱንም እሰጥሃለሁ። በተጨማሪም፣ አቶ አስፋ ድፋዬና አቶ አብተው ገብረየሱስ የአቶ መኩሪያን የቅርብ ረዳቶች ሆነው ለብዙ ዓመታት ስለሠሩ፣ እነሱንም መጠየቅ ነው። በእነዚህ በጠቀስኩልህ ሰዎች ብቻ ሳትወሰን፣ ከጸሐፊ ትዕዛዝ ጋር በቅርብ ይሠሩ የነበሩትንም እንደ ልጅ ፈለቀ እርገቱ የመሳሰሉትን ሁሉ ኢንተርቪዩ በማድረግ ሚዛኑ የተስተካከለ ታሪክ እንዲሆንልህ መጣር አለብህ .... " አሉኝ።

ከዚህ በላይ እንደተገለጸው፣ ጠቅላይ ሚኒስትር አክሊሉ ሀብተወልድ የሰጡኝ ተስፋና ማበረታቻ፣ ከፍ ያለ የሞራል ድጋፍ ስለሆነኝ፣ የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን የሥልጣን አነሳሥና አፈጻጸም ታሪክ ለመጻፍ አሰብኩ። ፓሪስ ደርሼ አዲሱ ሥራዬን ከጀመርኩ በኋላ፣ ለመጻፍ ያሰብኳቸውን ሁለት

---

* ዘውዴ ረታ በፓሪስ የኢትዮጵያ አምባሲ ሚኒስትር ካውንስለርነት የተሾመበት ጊዜ ነበር።

መጻሕፍቶች፤ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴን መንግሥት ታሪክና የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን ጉዳይ፤ ለወዳጆቼ ጋዜጠኞች ለአንድሬ ፎንቴን (André Fontaine) የለሞንድ (Le Monde) ጋዜጣ ዋና አዘጋጅና፤ ለበሺር ቤን ያህመድ (Bechir ben Yahmed) የዠን አፍሪክ (Jeune Afrique) ሳምንታዊ መጽሔት ፕሬዚዳንት አማከርኳቸው። እንደ አጋጣሚ እነዚህ በዓለም ላይ ዝነኛ የሆኑት ታላላቅ ጋዜጠኞች፤ ተመሳሳይ የሆነ ሐሳብ ሰጡኝ። " ... የወልደጊዮርጊስን ጉዳይ፤ ከቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መንግሥት ታሪክ ለብቻ ነጥሎ ማቅረቡ ምንም ዓይነት ጥቅም አያመጣም። የኤርትራ ጉዳይ ግን፤ በኢንተርናሽናል ሸንጎ ላይ ብዙ ክርክር የተደረገበትና የተወሰነ በመሆኑ፤ ለብቻው አንድ መጽሐፍ ማዘጋጀቱ የተገባ ይሆናል ... " ሲሉ መከሩኝ።

እኔም ከአዋቂዎቹ በተሰጠኝ ምክር ተስማምቼ ጥናቴን ሳካሂድ፤ በአገራችን የደረሰው ለውጥና የደርግ መምጣት ሕይወቴን ስለአመሳቀለው፤ ለአሥራ ሰባት ዓመታት የሥነ ጽሑፍ እቅዴን አቋረጠው። ሆኖም የስደቱን አስቸጋሪ ሕይወት ከመጀመሬ በፊት፤ የሰበሰብኳቸውን ሰነዶች በሥርዓት ይገኑአቸው ስለነበረ፤ ከዚህ በፊት ለጻፍኳቸው ሁለት መጻሕፍቶች (የኤርትራ ጉዳይና፣ ተፈሪ መኰንን) እንዲሁም ዛሬ ላዘጋጀሁት የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መንግሥት ታሪክ በጣም ረድተውኛል። በዚህም መሠረት፤ ስለ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ሥልጣንና ሽረት፤ ጠቅላይ ሚኒስትር አክሊሉ ሀብተወልድ እ.ኤ.አ በመስከረም 1971 ዓ.ም ፓሪስ ላይ ለአሥር ቀናት አብሬአቸው በሰነበትኩባቸው ጊዜያቶች ውስጥ፤ የሰጡኝን ኢንተርቪዩ ከዚህ ቀጥሎ አቀርበዋለሁ።

## የአክሊሉ ሀብተወልድ አስተያየት

ጥያቄ - ጌታዬ ከፈቀዱልኝ የመጀመሪያው ጥያቄዬ፤ ከጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ጋር እንዴት እንደተዋወቃችሁና፤ አብራችሁ በሠራችሁበትም ዘመን፤ ስለነበራቸው ሥልጣን፤ ስለ አመራራቸውና ስለ ችሎታቸው፤ የእርስዎን አመለካከት እንዲገልጹልኝ ነው።

መልስ - እኔ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን ያወቅኳቸው፤ በስደቱ ዘመን እ.ኤ.አ በ1936 ዓ.ም በሎንዶን የጃንሆይ ልዩ ረዳት ሆነው በሚሠሩበት ጊዜ ነው። በፈረንሣይ አገር ትምህርቴን ከጨረስኩ በኋላ ጃንሆይ ለስደት ሲመጡ፤ በፓሪስ በኩል ሲያልፉና ከዚያም ወደ ሎንዶን ሲሻገሩ፤ ከአቶ ሎሬንሶ ታዕዛዝ ጋር (ኋላ ብላቴን ጌታ) ሆኜ አንዳንድ አገልግሎት በመስጠት ላይ ነበርኩ። ወዲያውም፤ ፓሪስ ለሚገኘው ለኢትዮጵያ ለጋሲዮን አንደኛ ጸሐፊና ፕሬስ አታሼ ሆኜ እንድሠራ የጃንሆይ ፈቃድ ሆነ። ቀጥሎም ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር የነበሩት ብላቴን ጌታ ወልደማርያም፤ ከጣልያን ጋር ዕርቅ አድርገው ሲለቁ፤ እኔ የለጋሲዮኑ ጉዳይ ፈጻሚ ሆኜ ለአራት ዓመታት በሠራሁበት ጊዜ፤ የጃንሆይ ልዩ ረዳት ከሆኑት ከአቶ ወልደጊዮርጊስ ጋር የቅርብ ግንኙነት ነበረኝ። ስለ ለጋሲዮኑ ሥራና ስለ ጊዜው የፖለቲካ ሁኔታ ቢያንስ በወር ሁለት ጊዜ ለምልከው ራፖር፤ በጃንሆይ ማሕተም መልሱን ከአስተያየትና ከመምሪያ ጋር የሚሰጡኝ እሳቸው ነበሩ። በዚያ በአስቸጋሪው ዘመን እኔ እንደአየሁት፤ ጃንሆይ የስደተኛ መንግሥት አቋቁመው ቢሆን ኖሮ፤ ያለ ጥርጥር አቶ ወልደጊዮርጊስን የጽሕፈት ሚኒስትር ያደርጓቸው ነበር። ነፃነት ሲመለስም፤ ጃንሆይ ወልደጊዮርጊስን የሾሟቸው ይህንን ሲሠሩት

የቆዩትን የጽሕፈት ሚኒስትርነትን ተግባር ስለሆነ፤ ለሥራው እንግድነት አልተሰማቸውም።

የኢትዮጵያ ነፃነት እንደተመለሰ፤ ለአንድ ዓመት ያህል በጦርነቱ ምክንያት ከአውሮፓ መውጫ በማጣት ከተንላላሁ በኋላ ወደ አገሬ ስመለስ፤ በዚያ በስደቱ ዘመን በሥራ የማውቃቸው አቶ ወልደጊዮርጊስ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ተብለው የጽሕፈት ሚኒስትር፣ አቶ ሎሬንሶ ብላቴን ጌታ ተብለው የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ሆነው ደረስኩ። አዲስ አበባ ከአረፍኩበት ከ "እቴጌ" ሆቴል ጸሐፊ ትዕዛዝ አውቶሞቢል ልከውልኝ ጃንሆይ ዘንድ ቀርቤ እጅ ስነሣ፤ ጃንሆይ የመጀመሪያው ጥያቄያቸው "መኮንን ሀብተወልድ የት ነው?" የሚል ነበር። እኔ እስከማውቀው አቶ መኮንን ከወንድማችን ከአቶ መክብብ ጋር ከፈረንሣይ አገር በመርከብ ተሳፍሮ ወደ ደቡብ አፍሪካ ጉዞ መጀመሩንና፤ ከዚያም በሌላ መርከብ እስከ ጂቡቲ መጥቶ በባቡር አዲስ አበባ ለመግባት ማሰቡን ነው አልኳቸው። ይህን በምልበት ጊዜ አጋጣሚ ሆኖ የእልፍኝ አስከልካዩ ሻለቃ መርዕድ መንገሻ አንድ ቴሌግራም ይዘላቸው መጣ። ቴሌግራሙ አቶ መኮንን ከደቡብ አፍሪካ ለጃንሆይ የላከው ነው። " በእግዚአብሔር ቸርነት ደቡብ አፍሪካ ደርሼ ወደ ጂቡቲ የሚያመጣኝን መርከብ በመጠባበቅ ላይ ነኝ። ቦታ ለማግኘት አንድ ወር ይፈጃል እያሉ ያስፈራሩኛል። እንግዲህ የግርማዊነትዎ አምላክ ይርዳኝ! " የሚል ነው። ጃንሆይ በደረሳቸው ቴሌግራም በጣም ተደሰቱ። እኔንም ጥቂት ቀናት ላስብበትና ሥራ ላይ እመድብሀለሁ። እስከዚያም ለመኖሪያህም ሆነ ለትራንስፖርት የሚያስፈልገው ወጭ ሁሉ ይሰጥሃል ብለው አሰናበቱኝ።

አንዳንድ የድሮ የምኒልክ ትምህርት ቤት ጓደኞቼን አገኘሁ። ይልማ ዴሬሣ የገንዘብ ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር ሆኖ ከበላዩ ሚኒስትር ሳይሾምበት ይሠራል። ጌታሁን ተሰማ የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር ሆኗል። መሸሻ ኃይሌ የሥራ ሚኒስቴር ዲሬክተር ተብሏል። ወንድሜ አካለወርቅ የቢሾፍቱ ገዥ ነው። እነዚህን ሁሉ በየቀኑ አገኛቸው ነበር። እኔ መሥራት የምፈልገው ውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር መሆኑን ለጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ነግሬአለሁ። ጃንሆይም ይህንኑ ፍላጐቴን መስማታቸውን ጌታሁን ነግሮኝ ነበር። ሎሬንሶ ታዕዛዝ አረፍኩበት ሆቴል ድረስ መጥተው፤ የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር ሆነህ ከእኔ ጋር እንድትሠራ ለጃንሆይ ነግሬአቸዋለሁ አሉኝ። ይሁን እንጂ፤ መልሱን ከጃንሆይ አላገኙም። በመካከሉ ብዙ ቀን አለፈ። ከወር ወደ ሁለት ወር ተቃረበ። በመጨረሻው፤ ለእኔ ሥራ መስጠት አልተፈለገም ብዬ አሰብኩ። ለሆቴልና ለመኖሪያዬ ያለኝም ገንዘብ እየመነመነ ሄደ። ስለዚህ፤ ያለ ሥራና ያለ ገቢ እዚህ ምን አደርጋለሁ? ብዬ ወደ አውሮፓ ለመመለስ ወሰንኩ። ይልማ ዴሬሣ፤ ጃንሆይ በየሳምንቱ ቅዳሜ ቢሾፍቱ ስለሚሄዱ፤ እዚያ ተገኝተህ አነጋግራቸው አለኝ። ወንድሜ አካለወርቅም በዚህ ሐሳብ ተስማምቶ ቢሾፍቱ ይዞኝ ሄደ። መንገድ ላይ ሆኜ ስጠባበቅ ጃንሆይ አውቶሞቢላቸውን አቁመው፤ እዚህ ምን አመጣህ? ብለው ጠየቁኝ። ችግሬን በአጭሩ አስረዳኋቸው። ሰኞ ጠዋት ቤተመንግሥት እንድትመጣ አሉኝ። ለእልፍኝ አስከልካያቸው ለሻለቃ መርዕድም ነገሩት። እንደታዘዝኩት ሰኞ ጠዋት ቤተመንግሥት ስደርስ፤ የግቢው አሽከሮች እየገፋፉኝ ወደ ሹመት መስጫ ቤት ወሰዱኝ። ብዙዎች ነበርን። ሹመት ነጋሪው ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ናቸው።

- ብላቴን ጌታ ሎሬንሶ ታዕዛዝ የፖስታ ሚኒስትር፣
- ይልማ ዴሬሣ የገንዘብ ም/ሚኒስትር፣
- አክሊሉ ሀብተወልድ የጽሕፈት ም/ሚኒስትር፣
- ብላታ ኤፍሬም ተወልደ መድህን የውጭ ጉዳይ ም/ሚኒስትር፣
- ጌታሁን ተሰማ የአገር ግዛት ዋና ዲሬክተር፣
- አካለወርቅ ሀብተወልድ የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር

ተብሎ የሹመቱ አዋጅ ተነገረን። እንደ እውነቱ ከሆነ፤ እኔ ምንም ከማላውቅበት ከጽሕፈት ሚኒስቴር ም/ሚኒስትርነት አንድ ደረጃ ዝቅ አድርገው ውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር ቢሉኝ፤ ደስታውን አልችለውም ነበር። ከዚያ ወደ ጃንሆይ ዙፋን ተወስደን እጅ ከነሳን በኋላ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ለብቻዬ ጠርተው፤ " .... እዚህ ባላገር ከሆነ ሚኒስቴር ውስጥ እኔ ምን አደርጋለሁ? ብለህ እንደምትበሳጭ አውቃለሁ። ትዕግሥትህን አጠንክር! የታሰበልህ ሌላ በጣም የምትወደው ሥራ ይጠብቅሃል ... " አሉኝ። በዚህ ከጸሐፊ ትዕዛዝ በተሰጠኝ ምክር ለጥቂት ወራት በትዕግሥት ከተጠባበቅኩ በኋላ፤ እንዳሉትም ልክ ለይልማ ዴሬሣ እንደተደረገው እኔም የውጭ ጉዳይ ምክትል ሚኒስትር ተብዬ ከበላዬ ሚኒስትር ሳይሾም የካቢኔው አባል ሆንኩ። እንግዲህ! ከጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ጋር የተዋወቅነውና አብረን መሥራት የጀመርነው፤ እ.ኤ.አ በ1936 ዓ.ም ሲሆን፤ ለአሥራ ዘጠኝ ዓመታት ከኖርን በኋላ፤ የሥራ ግንኙነታችንና እንዲሁም የነበረን ቅርበት የተቋረጠው፤ እሳቸው የአሩሲ ጠቅላይ ገዥ ሆነው ሲሾሙ፤ እ.ኤ.አ በ1955 ዓ.ም ነው።

እንግዲህ! እኔ ያውቅኳቸው ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ፤ በችሎታቸው የሚተማመኑ፣ በሥልጣናቸው ሳያመነቱ የሚወስኑ፣ ማንንም የማይፈሩ፣ የተፈጥሮ ብልህነት ያላቸው ጠንካራ ሠራተኛ ናቸው። ነፃነታችን እንደተመለሰ፤ የጽሕፈት ሚኒስትር ከሆኑ ከሁለት ዓመት በኋላ፤ ለስድስት ዓመታት የአገር ግዛት ሚኒስቴርን፤ ለሌላ ስድስት ዓመታት ደግሞ የፍርድ ሚኒስቴርን ደርበው ሲመሩ፤ ሥልጣናቸውን በብዙ አሳድገውታል። ተደማጭነታቸውም በሁሉም ዘንድ ተቀባይነት እንዲያገኝ አስደርገዋል። ለብዙ ሰዎች፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ በሥልጣን ከሌሎቹ ሚኒስትሮች ሁሉ ገናና ያደረጋቸው፤ በጽሕፈት ሚኒስትርነታቸውና የንጉሠ ነገሥቱን ትልቁን ማሕተም ያዥ በመሆናቸው መስሎ ይታያቸዋል። እንደ እኔ ከሆነ ይህ አስተያየት ልክ አይደለም። የጽሕፈት ሚኒስትር ቦታ፤ ከወልደጊዮርጊስ በፊት የተመሠረተና ከወልደጊዮርጊስም በኋላ የቀጠለ መሥሪያ ቤት ነው። ነገር ግን፤ ወልደጊዮርጊስ የያዙትን ሥልጣን ከእሳቸው በፊት የነበሩትም ሆኑ ከእሳቸው በኋላ የተሾሙት፤ የእሳቸውን ያህል ዕድል ያገኙ የሉም። ስለዚህ በእኔ አስተያየት፤ የጽሕፈት ሚኒስቴርን ሥልጣን በዘመኑ የፈጠሩትም፤ ያሳደጉትም፤ ያስፋፉትም ራሳቸው ወልደጊዮርጊስ ናቸው

እንጂ፤ ከንጉሠ ነገሥቱ ታስቦበት ወይም ተዘጋጅቶ የተሰጣቸው አይደለም። ሰውየው ብልህ በመሆናቸው፤ ሥልጣንን ለማሳደግም ሆነ ለማስፋፋት ብዙ ዘዴ ነበራቸው። ለምሳሌ፤ ከጽሕፈት ሚኒስትርነታቸው ጋር ለስድስት ዓመታት ይዘውት የነበረው የአገር ግዛት ሚኒስቴር ለሌላ ሰው ሲሰጥባቸው፤ ከእንግዲህ ወዲህ የወልደጊዮርጊስ የሥልጣን ገናናነት አልቆለታል። የፖሊስ ኃይልና ፀጥታ ከእጃቸው ከወጣ፤ ሌላ የማስፈራሪያ ኃይል አይኖራቸውም ተብሎ ተጨብጭቦ ነበር። እሳቸው ግን ሁለት ሳምንት ባልሞላ ጊዜ ውስጥ ለሥልጣናቸው ኃይል ሌላ መንገድ ቀይሰውለት ብቅ አሉ። ለጽሕፈት ሚኒስቴር ተግባር ቀድሞ ያልነበረ አዲስ ኃላፊነት በማስጨመር፤ የየሚኒስቴሩን ሥራ የመቆጣጠርና የማስተባበር ሥልጣን ተሰጣቸው። እንግዲህ! ቀደም ብዬ እንደገለጽኩት፤ አሁንም የምደግመው፤ በእሳቸው ዘመን ጽሕፈት ሚኒስቴር የተሰጠውን ሥልጣን፤ ከእሳቸው በፊት የነበሩት ጸሐፊ ትዕዛዞች ሁሉ ኖርዋቸው እንደማያውቅና፤ ከእሳቸውም በኋላ የተሾምነው አቶ ተፈራ ወርቅና እኔ አክሊሉ ሀብተወልድ፤ የእሳቸውን ግማሽ እንኳን ሥልጣን እንዳላገኘን ለማንም በግልጽ መታወቅ ያለበት መሆኑን ነው።

ጥያቄ፤ ማንም ሰው እንደሚያውቀው፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ እንደብዙዎቹ የኢትዮጵያ ታላላቅ ሰዎች ሁሉ የአካዳሚ ዘመናዊ ትምህርት አላገኙም። ነገር ግን ፈረንጅ አገር ተልከው ከፍተኛ የዩኒቨርሲቲ ትምህርት ከፈጸሙት ሰዎች ይልቅ፤ ሥራ የመምራትና የመቆጣጠር ችሎታቸው ከፍ ያለ ሆኖ ይታያል። የዚህ ምክንያቱ ምንድን ነው?

መልስ፤ ይህ ጥያቄ አንድ ቀን አቶ መኰንን የነገረኝን ምሳሌ አስታወሰኝ። " ... አንድ ሰው ሳያስበውና ሳይጠብቀው ትልቅ ሹመትና ሥልጣን ከተሰጠው፤ ሌሊቱን አዋቂና ጥበባዊ ሆኖ ያድርና ጠዋት ሲነሣ የተማረውም ያልተማረውም እኩል ሊሰግዱልኝ ይገባል፤ ብሎ ይጠብቃል ... " አለኝ። እንግዲህ በዚህ መንፈስ፤ አንድ ሰው ሥልጣን ሲይዝ ችሎታውም አብሮ ይፈጠራል ማለት ነው። ይህ ምሳሌ እንኳ ለጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ የሚጠቀስ አይደለም። እሳቸው በዘመናቸው የአካዳሚ ትምህርት የማግኘት ዕድል አልገጠማቸውም። ይህን ዕድል አግኝተው ቢሆን ኖሮ፤ በዚህ ተፈጥሮአቸው ላይ ምን ዓይነት ሊቅ ይወጣቸው እንደነበረ ይሰማኛል። ሆኖም አእምሮአቸው ብሩህ በመሆኑ፤ ነገርን የመረዳት፤ ተረድቶም የማስረዳት ችሎታቸው ከፍ ያለ ስለሆነ፤ ፈረንጅ አገር ባለመማሬ የጐደለኝ ነገር አለ ብለው የሚጸጸቱ አልነበሩም። ለምሳሌ፤ በሥራ ላይ አንድ ያላወቁት እንዲያውም ከዚህ ቀደም ያልሰሙት ነገር ቢያጋጥማቸው፤ በጥቂት ጊዜ ውስጥ አጥንተው ይደርሱበትና ለውሳኔው ይዘጋጁበታል እንጂ፤ የማላውቀው ጉዳይ ነው ብለው ለሌሎች እናውቃለን ለሚሉት አይለቁላቸውም። በሥልጣን አያያዝና አጠቃቀምም ረገድ፤ ማንም የማይወዳደራቸው ኃይለኛ ናቸው።

ጥያቄ፤ እንግዲያውስ! ምንም ብልህና ጠንካራ ሠራተኛ ቢሆኑ፤ ይህ ዓይነቱ የሥልጣን አጠቃቀምና ኃይለኝነታቸው፤ ዲክታተር አያሰኛቸውም ወይ?

መልስ፤ ይኸማ፤ የተደበቀ ምሥጢር አይደለም። ጸሐፊ ትዕዛዝ፤ በአሠራራቸውም ሆነ በአመራራቸው ዲክታተር ናቸው። ይህንን እሳቸውም አይክዱም። እንደ አንዳንዶቹ እኔ ወልደጊዮርጊስ "ሊበራል" ነኝ ብለው ፎክረው አያውቁም። የሚያምኑበትን ለመፈጸም ወደ ኋላ የማይሉ፤ ለማንም የማይበገሩ ናቸው። ሲፈልጉ ደግ መሆን ይችላሉ። ሲፈልጉ ደግሞ ጨካኝ መሆን ይችላሉ። ሰው ሁሉ የሚፈራቸው በዚህ ምክንያት ነው።

ጥያቄ፤ እስካሁን የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን የአሠራር ጠባያቸውንና የሥልጣን አጠቃቀማቸውን አየን። አሁን ደግሞ፤ በሠሩበት ዘመን ስለአበረከቱት አገልግሎት ጌታዬ የሚያውቁትን ዋና ዋናዎቹን ጉዳዮች ቢገልጹልኝ ጠቃሚ ይመስለኛል።

መልስ፤ እኔ መቸም እርግጠኛ ሆኜ መናገር የምችለው፤ በሥራ አብረን በኖርንበት ዘመን የማውቀውን ነው። በተጨማሪም ከእኔ በፊት ጸሐፊ ትዕዛዝን የሚያውቋቸው አንዳንድ ሰዎች የሰጡትን አስተያየት ልጠቅስ እችል ይሆናል። ለእኔ እንደሚታየኝ የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ የሥራና የአገልግሎት ታሪክ የተወሳሰበ አይደለም። ባጭሩ ሲጠቃለል፤ ከሆስፒታል አስተርጓሚነት ወደ ውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር፤ ዲፕሎማትነት፤ ከዚያም በሹመት ወደ ጽሕፈት ሚኒስቴር ተዛውረው፤ ለአሥራ አራት ዓመታት ከጃንሆይ ጋር በከፍተኛ የሚኒስትርነት ደረጃ የሠሩ መሆናቸው ነው። በእኔ በኩል ለአገልግሎታቸው የተለየ አክብሮት የምሰጠው፤ በሁለት ዋና ዋና ጉዳዮች ላይ ነው። ይኸውም የመጀመሪያው፤ ነፃነታችን እንደተመለሰ እንግሊዞች ቅኝ ግዛታቸው ለማድረግ የፈጠሩብንን ከፍተኛ ችግር ለማስወገድ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ እንዴት ባለ ጥንካሬ እንደታገሉ ሲሆን፤ ሁለተኛው ደግሞ ኤርትራን ወደ ኢትዮጵያ ለማስመለስ በአገር ውስጥ ሳጋጠመን ችግር ሁሉ መፍትሔ እየሰጡ፤ እኛም በዓለም ጉባኤ ላይ ለምናደርገው ሙግት፤ ምን ያህል ይረዱንና ምን ያህል ሥራችንን ያቃኑልን እንደነበረ በማስታወስ ነው። ይህንን የምነግርህ ባጭሩ ነው። ዝርዝሩ ግን ብዙ ነው። ከዚህ በቀር ደግሞ መረሳት የሌለበት የኢትዮጵያ ነፃነት በፋሽስት እጅ በወደቀበት ዘመን፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ የሰጡት ከፍተኛ አገልግሎት ነው። ጃንሆይ በጦር ሜዳ ሲዋጉና ከዚያም ወደ ስደት ሄደው ነፃነታችን እስከተመለሰበት ጊዜ ድረስ፤ ንጉሠ ነገሥቱን ያልተለዩና በጠነከረ መንፈስ ከልብ የደከሙ ናቸው። አቶ መኰንን ሀብተወልድ፤ ለእኔና ለወንድሞቼ ሲያጫውተን፤ "... ጃንሆይ በዚያ በአስቸጋሪው የስደት ዘመን፤ ወልደጊዮርጊስን የመሰለ ጠንካራ ሠራተኛ አጠገባቸው ባያገኙ ኖሮ፤ ብዙ ችግር ይደርስባቸው ነበር። በኢትዮጵያ ግዛት ውስጥ ከጠላት ጋር ከሚዋጉት አርበኞቻችን ጋር ግንኙነት ዘርግቶ፤ በየጊዜው የሚከናወነውን የነፃነት ትግል፤ ለጃንሆይ በማቅረብና ምራላቸውን በማጠናከር፤ አርበኞቹ ደግሞ ተስፋ ሳይቆርጡ ትግላቸውን እንዲቀጥሉ፤ ከጃንሆይ የሚሰጣቸውን አስደሳች መምሪያና ማበረታቻ እያዘጋጀ በመላክ፤ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ የፈጸመው ሞያ የሚረሳ አይደለም... " ብሎናል። ይህ አቶ መኰንን ሀብተወልድ የገለጸልን አስተያየት ያየውንና የሚያውቀውን ስለሆነ፤ ለታሪክ ምስክር ሆኖ የሚቀርብ ነው። እኛም ከእነ አቶ መኰንን ሀብተወልድ ቀጥሎ ለአገራችን ኃላፊነትን የተቀበልን ሰዎች፤ የኢትዮጵያ ነፃነት ከተመለሰ

በኋላ፣ መንግሥት ሲቋቋምና የአገር አስተዳደር ሲመሠረት፣ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ የንጉሠ ነገሥቱ ቀኝ እጅ ሆነው የተዘረጉትን ሥራዎች ሁሉ የሚያንቀሳቅሱ ሞተር እንደነበሩ፣ ምስክርነታችንን እንሰጣለን። እርግጥ ነው፣ በዚህ በተዘረዘሩት ሥራዎቻቸው ብዙዎቹ ቢያደንቋቸውም፣ ሌሎች ደግሞ "ኃይለኛ ዲክታተር" በማለት የሚጠሏቸው እንደነበሩ አይካድም። የሥራዎቻቸው ውጤት ሲመዘን ግን፣ የሚከብዱት ፍሬዎቹ ናቸው እንጂ፣ ገለባዎቹ አይደሉም።

ጥያቄ፣ ጌታዬ ሰፋ አድርገው ያስረዱኝ የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ አገልግሎት የሚከበር ነው። የሚያሳዝነኝ እኛ በማስታወቂያ ሚኒስቴር ሥራ ላይ ብዙ ዓመታት የኖርን ሰዎች ይህን የመሳሰሉት ሰነዶች የሉንም። ወደተነሣሁበት ጉዳይ ልመለስና፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ የንጉሠ ነገሥቱ የቅርብ ረዳት ሆነው፣ ለአሥራ አራት ዓመታት ያንን ሁሉ ከፍተኛ ሥልጣን ይዘው ሲሠሩ ከኖሩ በኋላ፣ ምን ክፉ ነገር ቢያጋጥም? ምን ክፉ ነገር ቢደርስ? ከጃንሆይ ጋር ለመለያየትና ለሽረት በቁ? ....

መልስ፣ መቸም የመንግሥት ሠራተኞች በሆኑት ዘንድ ሲወራ የኖረውን ታውቀዋለህ። "ሀብተወልድ ወንድማማቾች" ወልደጊዮርጊስን ከንጉሠ ነገሥቱ ጋር አጣልተው አሻሯቸው እየተባለ በሰፊው ተወርቷል። ጸሐፊ ትዕዛዝም ይህንን ሰምተው፣ ከአካለወርቅ በስተቀር በሌሎቻችን ላይ ከፍ ያለ ጥላቻ አሳድረዋል። ይኼ በጣም ያሳዝናል። ይሁን እንጂ፣ እውነቱ አንድ ቀን ተገልጦ እንደሚወጣ ብዙ ተስፋ አደርጋለሁ። ገና ከመሻራቸው ከስድስት ወር በፊት፣ ጃንሆይ አውሮፓን በሚጐበኙበት ጊዜ ፓሪስ ሆነን ጸሐፊ ትዕዛዝ እኔን ምን እንዳሉኝና እኔም ምን እንደመለስኩላቸው ነግሬሃለሁ። ባጭሩ ለማስታወስ ያህል ጸሐፊ ትዕዛዝ የተናገሩኝ፣ " ... አንተና ወንድምህ መኰንን ሀብተወልድ ዘመዳችሁን ሣህሉ ድፋዩን ጨምራችሁ እኔን ከጃንሆይ ጋር ለማጣላትና ለማሻር የምትሠሩትን ተንኰል ደርሼበታለሁ ... " ብለው ነው። እኔ ለዚህ መሠረት ለሌለውና ፍጹም ውሸት ለሆነ ወሬ የእግዚአብሔርን ስም ጠርቼ መልሱን በሚገባ ሰጥቻቸዋለሁ። ስለዚህ፣ ሕሊናዬን የሚወቅሰኝና የሚቆጨኝ ነገር የለም።

አቶ መኰንን እና ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወዳጅነታቸው የተጀመረው፣ ጠላት ኢትዮጵያን ከመያዙ በፊት መሆኑን ሁለቱም ዘርዝረው ነግረውናል። ፋሽስት ከአገራችን ተባርሮ ነፃነታችን ከተመለሰም በኋላ፣ ወዳጅነታቸውና መግባባታቸው እየጋለ በመሄዱ፣ በአንድ ዓይነት አሠራርና በአንድ ዓይነት መንፈስ ጃንሆይን እያገለገልን፣ ኢትዮጵያ አገራችንን ከጨለማ ሕይወቷ አውጥተን ወደፊት እናራምዳታለን ብለው ተነሱ። ጃንሆይም እነዚህ ሁለቱ እንደ ወንድማማች የተሠለፉት ሰዎች፣ አሠራራቸውና አገልግሎታቸው ስለጣማቸው፣ እንዲቀጥሉበት አተጓቸው። እነሱም፣ ጃንሆይ ከእኛ ጋር ስለሆኑ ማን ይደፍረናል? ማንስ ይቋቋመናል? የሚል ዕምነት አደረባቸው። በእውነትም እነሱ ሁለቱ የማይፈቅዱትን ባለሥልጣን ጃንሆይ አይሾሙም። እነሱ ሁለቱ የማይስማሙበትን ማናቸውንም የአገር ጉዳይ ጃንሆይ አያጸድቁም። በእነሱ በሁለቱ ላይ ተቃውሞውን የሚገልጽ ወይም እየነቀፈ የሚተች ሚኒስትር፣ በቦታው ላይ መቆየት አይችልም። ለምሳሌ ጓደኞችን መኰንን ደስታ ከነፃነት መመለስ በኋላ፣ የመጀመሪያው የትምህርት ሚኒስትር ነበር። በዚህ ሥራ ላይ

በነበረበት ጊዜ፣ አስፈላጊ ባልሆነ ምክንያት ከጸሐፊ ትዕዛዝና ከአቶ መኰንን ጋር ተጋጩ። እነዚህ ሁለቱ ሰዎች ጃንሆይን በእጃቸው አድርገው ለአገራችን እርምጃ እንቅፋቶች ሆነዋል የሚል አስተያየት በግልጽ መናገር ጀመረ። አንድ ጊዜ ቢቸግረን እኔና ወዳጄ ኰሎኔል ክፍሌ ዕርገቱ (ኋላ ደጃዝማች) ወንድማችንን እንምከረው ብለን እቤቱ ሄድን። እኛ የመከርነው፣ እነሱን ተለማመጥ፣ ወይም እጅ ንሣ አልነበረም። ይህንን በእነሱ ላይ የምትነዛውን ነቀፌታ አቁም። ምንም አይጠቅምህም በማለት ነበር። በጣም አስገራሚ የሆነ መልስ ሰጠን። " ... መጀመሪያ እናንተ ሁለታችሁም ጥሩ ዳኞች አይደላችሁም። እክሊሉ የመኰንን ሀብተወልድ ወንድም ነህ። ክፍሌም የትልቁ ባለሥልጣን የወልደጊዮርጊስ ቀኝ እጅ ስለሆንክ ያው ወንድም ነህ ማለት ይቻላል። ስለዚህ፣ እነዚህ ሁለት አምባገነኖች ወልደጊዮርጊስና መኰንን ሀብተወልድ የሚሠሩትን ግፍ ከእናንተ ጋር መወያየት አይቻልም። እኔ ደግሞ ነፃነቴን በጣም እወዳታለሁ። ያለችኝ አቅም እሷ ብቻ ስለሆነች፣ እስከ መጨረሻው በእሷ እጠቀማለሁ። ይህችን አለኝታዬን አምባገነኖቹ አንድ ቀን ሲመቻቸው ይነጥቁኝ ይሆናል። እስከዚያ ድረስ ግን ያለኝን ዕምነት ይገፌ መናገሬን አላቋርጥም ... " ብሎ አሰናበተን። ጓደኛችን የሚወቅሰው ብዙውን ጊዜ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝንና አቶ መኰንንን ብቻ ሳይሆን፣ ጃንሆይንም አይምርም ነበር። መቸም በዚህ ብቸኛ በሆነው አቋሙ ጉዳትን እንጂ ሰላምን አላገኘም። ጠባዩን ምክንያት እያደረጉ፣ ከትምህርት ሚኒስቴር አንሥተው ፖስታ ሚኒስቴር ላኩት። ከዚያም እንደማስታውሰው የወሰጋ ገኘር አደረጉት። ከዚያ ደግሞ አምጥተው ከቄሶች ጋር የቤተክህነት ሥራ አስኪያጅ አሉት። ይህ ሁሉ መንከራተት ቢደርስበትም፣ መኰንን ደስታ ከሚያምንበት አልተነቃነቀም። ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና አቶ መኰንን ሀብተወልድ በሥልጣን እስከቆዩ ድረስ፣ መሥራት አይቻልም የሚለውን ነቀፌታ ቀጠለበት። እነሱም እንደፈለግህ ተናገር። ቢያሰኝህም ተሳደብ። ከእኛ ጋር እስከ አልተባበርክ ድረስ ምንም እንደማይሳካልህ እወቅ! ብለው መንገዱን ዘጉበት። ጓደኛችን ከባድ ሕመም ላይ እስከወደቀበት ጊዜ ድረስ፣ እንዲሁ እንደተማረረ፣ የሚያስበውን ሳይፈጽም፣ የሚመኘውን ማግኘት ሳይችል፣ ከዚህ ዓለም በሞት ተለየ። ጓደኛችንን መኰንን ደስታን ምንጊዜም የማልረሳው ሰው ነው። የማስታውሰውም ጥልቅ ከሆነ የሐዘን ስሜት ጋር ነው።

እንግዲህ! የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና የአቶ መኰንን ወንድማማችነት ለጃንሆይ ታማኝ በመሆን ላይ የተመሠረተ ስለሆነ፣ አንድነታቸው እስከ መቸ እንደሚቀጥል በዚያን ጊዜ አይታወቅም ነበር። በፖለቲካ ዓለም፣ በሁለት ሰዎች መካከል የሚገነባው መግባባትና መተባበር፣ እንክን ሳያደፈርሰው እስከ ሰዎቹ ሕይወት ፍጻሜ ድረስ እንደሚቆይ፣ እርግጠኛ መሆን አይቻልም። እዚህ ላይ፣ ወዳጄ ይልማ ዴሬሣ በአሜሪካ የኢትዮጵያ አምባሳደር በነበረበት ጊዜ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ከመሻራቸው አንድ ዓመት በፊት፣ በዋሽንግተን ተገናኝተን ራት እየበላን ስንጨዋወት፣ የተናገረው "ትንቢት" የሆነ አስተያየት ትዝ አለኝ። እሱም እንደ መኰንን ደስታ በዝንኞቹ በሁለቱ ባለሥልጣኖች ተጠቃሁ ባይልም፣ ድጋፍ እንዳልነበረው ያምናል።

ስማ፣ አክሊሉ አለኝ። " ... በእኔ ግምት የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና የአቶ መኮንን ፍቅር ከእንግዲህ ወዲህ ለአንድ ዓመት እንኳ አይቀጥልም። የመለያያቸው ጊዜው የተቃረበ ሆኖ ይታየኛል። እንደምታወቀው፣ እነዚህን ሁለት ሰዎች በሥልጣን በየደረጃው እያሳደጉ፣ እንዲስማሙና እየተደጋገፉ ጃንሆይን የሚጠቅም አገልግሎት እንዲሰጡ ያደረጓቸው ራሳቸው ጃንሆይ ናቸው። ወደፊትም፣ አጣልተው የሚያለያይዋቸው ጃንሆይ ራሳቸው ናቸው። በመጨረሻም፣ ከሁለቱ መካከል የሚያምኑትን አስቀርተው፣ የሚጠራጠሩትን ያባርራሉ። ይህንንም ስል፣ ታማኝ አድርገው የሚያስቀሯቸው ያንተን ወንድም ሲሆን፣ ተጠርጣሪውና ተጠቂው ወልደጊዮርጊስ ይሆናሉ ማለቴ ነው ... " አለኝ። እኔ አይመስለኝም አልኩት። " ... ጃንሆይ ምናልባት ፍቅራቸው ሲያልቅ ሁለቱንም ያባርራሉ እንጂ፣ አንዱን ለይተው አያስቀሩም። በልማዳቸው ከአዳዲስ ቡድን ጋር መሥራት ስለሚወዱ፣ ጊዜው ሲደርስ ሁለቱንም ሽረው በአዳዲሶች ይተኩዋቸዋል። በዚህ ጊዜ (በቀልድ) ... እኔንና አንተን ሊተኩን ይችላሉ ብለን ለምን ተስፋ አናደርግም? አልኩት ... " " ... አክሊል፣ አይምሰልህ፣ ጃንሆይ ለወልደጊዮርጊስና ለመኮንን ቦታ አንተንና እኔን አያጩንም። ደግሞም ጃንሆይ በተዓምር ካልተለወጡ በስተቀር፣ ወልደጊዮርጊስና መኮንን ሳስለመዷቸው አሠራር፣ አንተና እኔ አናጠግባቸውም። ለማናቸውም፣ ይልማ ምን አለ? በለኝ ከእንግዲህ ወዲህ ጸሐፊ ትዕዛዝ የአንድ ዓመት የሥልጣን ዕድሜ የላቸውም ... " አለኝ። " እስከዚህ እርግጠኛ ሆነህ ለመናገር ምንጭህ (Source) ምንድን ነው? " ብዬ ጠየቅኩት። " ... እኔ ከማንም ሰው አልሰማሁም። ዋሽንግተን እየኖርኩ፣ ከአዲስ አበባ ጋር የተለየ የመገናኛ አንቴና አልዘረጋሁም። የተናገርኩት ለእኔ የታየኝን እና የተሰማኝን ነው። አንተ ማመን የለብህም። እኔ በዕምነቴ እረጋለሁ" ብሎኝ ተለያየን።

እንግዲህ፣ አንተ ላቀረብካቸው ጥያቄዎች ቀጥተኛውን መልስ የምትጠብቀው፣ ጃንሆይ ጸሐፊ-ትዕዛዛቸውን የሻሩበትን ምክንያት ለማወቅ ነው።

በዚህ ጉዳይ እኔ የምናገረው የማንም ወገን ሆኜ አይደለም። የምናገረው ራሴ የደረስኩበትንና የማምንበትን ነው። ጸሐፊ ትዕዛዝ በተሻሩ ጊዜ፣ በአዲስ አበባ ከተማ የተነገረውንና የተወራውን ታስታውሳለህ! በጃንሆይ በኩል "ልብህም እግርህም ስለራቀን በተጨማሪም ሥራህን ችላ ስላልከው፣ ጠባይህን እንድታርም ነው" የሚል ምክንያት ተሰጥቷል። በውጭ ደግሞ፣ ቀደም ብዬ እንደጠቀስኩልህ፣ ሀብተወልድ ወንድማማቾች በተለይ አቶ መኮንን ጸሐፊ ትዕዛዝን ከጃንሆይ ጋር አጣልተው አሻሯቸው ተብሎ ተወርቷል።

ለእኔ፣ እነዚህ ሁሉ ምክንያቶች እንኳንስ በነጠላ፣ በመቶም ተባዝተው ቢቀርቡ፣ በጣም፣ በጣም፣ በጣም፣ ደካሞች ናቸው። የልብ መራቅ፣ የእግር ማጠር፣ ከሀብተወልዶች ጋር መጣላት፣ ያንን ሁሉ ሥልጣን ይዞ፣ ለብዙ ዓመታት የመንግሥቱን አስተዳደር ሲያንቀሳቅስ የኖረውን ትልቅ ሰው፣ እስከዚህ አዘቅዝቆ ለመሻር የሚያደርሱ ምክንያቶች አይደሉም።



አቶ አክሊሉ ሀብተወልድና አቶ ይልማ ደሬሣ በዋሽንግተን ተገናኝተው ስለ ኢትዮጵያ የአገር ውስጥ የፖለቲካ ጉዳይ ሲወያዩ፤ ይልማ ደሬሣ ስለ ጸ.ት ወልደጊዮርጊስ ከሥልጣን መነሳት የታያቸውን ተንብየዋል፤

በቀድሞው ዘመን በአንዳንድ አገሮች ላይ የደረሰውን ታሪክ ስንመለከት፤ መሪዎች ባለሟል እያደረጉና ሙሉ ሥልጣን እየሰጡ ካሳደጓቸው ሰዎች ጋር ፍቅራቸው እስከመጨረሻው አይዘልቅም። በመካከላቸው ያለው በጣም የመተዋወቅና የመቀራረብ ሁኔታ፤ ከጊዜ ብዛት አክብሮትንና ፍርሃትን እየቀነሰ፤ መደፋፈርን እያስከተለ ስለሚሄድ፤ በፍቅሩ ቦታ ጠብ ይተካና እስከ መለያየት ያደርሳቸዋል። በአንዳንድ አገሮች ላይ ደግሞ እንደደረሰው፤ መሪው መርጦ ያሳደገውና ከፍተኛውን ኃላፊነት የተቀበለው ሰው፤ ከጊዜ ብዛት ሥልጣኑን እያጠናከረ፤ በሕዝቡም ዘንድ ታዋቂነቱ እየገነነ ሲሄድ፤ መሪው ሥጋት ያድርበትና ሥልጣኑን ገፍፎ ያሰናብተዋል። እንግዲህ፤ እኔ የጃንሆይንና የጸሐፊ ትዕዛዝን ፍቅርና ጠብ የምመለከተው፤ በተለይ በዚህ በሁለተኛው ዓረፍተ ነገር በጠቀስኩት የታሪክ ኤክስፔሪያንስ ላይ ተመርኩዤ ነው። በዚህም መሠረት፤ የጃንሆይና የጸሐፊ ትዕዛዝ ጉዳይ ከጠቀስኩት የታሪክ ምሳሌ ጋር አንድ ዓይነት ነው ባልልም፤ በጣም የሚመሳሰልና የሚቀራረብ መሆኑን አምንበታለሁ።

ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ለአምስት ዓመታት ባለማቋረጥ፤ የየሚኒስቴሩን ሥራ የማስተባበርና የመቆጣጠር ሙሉ ሥልጣን ይዘው ሲመሩ፤ ጃንሆይ በምን ምክንያት ጠቅላይ ሚኒስትር ብለው እንዳልሾሟቸው፤ ለብዙ ሰዎች ግራ የሚያጋባ ነገር ሆኖ ነበር። ጸሐፊ ትዕዛዝም በዚህ ጉዳይ ያላቸውን እውነተኛውን ሐሳባቸውን አውጥተው ለወዳጆቻቸው ባይገልጹም፤ በቀልድ አድርገው ሲናገሩ እኔ እንደሰማኋቸው፤ " .. የየሚኒስቴሩን ሥራ የማስተባብረው እኔ ሆኜ፤ በምን ምክንያት የጠቅላይ ሚኒስትሩ ወንበር ባዶ ቦታ ላይ ብቻውን ሲሽከረከር እንደሚውል አልገባኝም ... " ይሉ ነበር።

ሁላችንም እንዳየነው፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ጠቅላይ ሚኒስትር አልተባሉም እንጂ፤ ሥልጣኑን መያዛቸው አልቀረም ነበር። በኦፊሲየል ጠቅላይ ሚኒስትር የተባሉት ቢትወደድ መኰንን እንዳልካቸው፤ በየሳምንቱ ማክሰኞ የሚደረገውን የሚኒስትሮች ስብሰባ ከመምራት በስተቀር፤ ሌላውን የየሚኒስቴሩን ኃላፊነትና ግዳጅ የሚቆጣጠሩት በጃንሆይ ስም ጸሐፊ ትዕዛዝ ናቸው። እኔ ከብዙዎቹ የካቢኔ አባሎች ጋር አልፎ አልፎ ስነጋገር፤ ጃንሆይ በተግባር የሚከናወነውን ሥራ እያጸደቁ፤ የጠቅላይ ሚኒስትርነትን ማዕረግ ለጸሐፊ ትዕዛዝ መስጠት ያልፈለጉበትን ምክንያት እናውቃለን የሚሉት ጥቂቶች አይደሉም። በእኔ ግምት፤ እኛ የካቢኔው ሚኒስትሮች በግልጽ መወያየቱን እየፈራን ነው እንጂ፤ ምክንያቱ ለምን እንደሆነ ለማወቅ አስቸጋሪ ሆኖብን አልነበረም። በዚያን ጊዜ ለእኔ እንደታየኝ፤ ጃንሆይ ጸሐፊ ትዕዛዝን ጠቅላይ ሚኒስትር ለማድረግ ያልፈለጉት፤ በሚቀጥሉት ምክንያቶች ነው ብዬ አምናለሁ።

1ኛ/ በአገር ውስጥ የሚወራው፤ የንጉሠ ነገሥቱን መንግሥት የሚያንቀሳቅሱት ትልቁ ዘውድ ቀረሽ ባለሥልጣን ወልደጊዮርጊስ ናቸው። እንደ ወንድሜ መኰንን አነጋገር ከሆነ፤ እሳቸው ያልባረኩት አይጸድቅም። እሳቸው የረገሙት አይድንም። ጃንሆይ፤ ስለ አገሩም ሆነ ስለ ሕዝቡ ጉዳይ የሚሠሩትና የሚወስኑት፤ በወልደጊዮርጊስ ሐሳብ ብቻ እየተመሩ ስለሆነ፤

ምንም ሥልጣን የላቸውም እየተባለ ነው። ይህ ሁሉ የሚወራው እንደ አሉባልታ የሚቆጠር ቢሆንም፤ ጃንሆይን ቅር ስለሚያሰኛቸው ለወልደጊዮርጊስ ጠቅላይ ሚኒስትርነቱን ከመስጠት ያለ ጥርጥር አግዷቸዋል።

2ኛ/ ንጉሣዊው ቤተሰብና መሳፍንቱ ደግሞ፤ ወልደጊዮርጊስ የጫኑት የሥልጣን ፈረስ የሚጋልበው እስከየት ድረስ ነው? ማገጃ ካልተደረገለት ከቤተመንግሥቱ ጉልላት ለመጢጋት ምን ቀረው? እያሉ፤ ጠዋትና ማታ ጃንሆይን ከማስቸገር አላቋረጡም። የንጉሣዊው ቤተሰብና የመሳፍንቱ ዋና ጥረት፤ ጃንሆይ ወልደጊዮርጊስን ከያዙት ከፍተኛ ቦታ አንስተው፤ ምንም ሥልጣን ወደሌለበት ሥፍራ እንዲያዛውሯቸው ነው። ሌሎቹ ቀርተው እኛ ቅድስት የሆኑት እቴጌ መነን እንኳ፤ ስለ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ የሥልጣን ኃይል በሚሰሙት በጣም ይሠጉ ስለነበረ፤ ጃንሆይ ከአጠገባቸው እንዲያርቋቸው ይፈልጉ ነበር። የጸሐፊ ትዕዛዝ ሽረት በተከናወነበት ዕለት፤ ግርማዊት እቴጌ በአረንጓዴው ሳሎን ከጃንሆይ አጠገብ አልለይም ብለው እስከመጨረሻው ድረስ የቆዩት፤ ጉዳዩ በሰላም አያልቅ ይሆናል ብለው በመሥጋት መሆኑን፤ ዋናው የእልፍኝ አስከልካይ ኮሎኔል መኩንን ደነቀ አጫውቶኛል።

3ኛ/ በውጭው ዓለም በተለይም በአውሮፓ በሚታተሙት ጋዜጦችና መጽሔቶች ላይ፤ በኢትዮጵያ የአስተዳደሩ ሥልጣን የተያዘው በአንድ ሰው እጅ ነው። ይህም ኃይለኛው ሰው ስሙ፤ "ወልደጊዮርጊስ" ነው። እየተባለ በተከታታይ የሚጻፈው አርቲክል፤ ጃንሆይን የሚያሳስባቸው መሆኑ ለማንም ግልጽ ነበር። እርግጥ ነው፤ ይህ ዓይነቱ ፕሮፓጋንዳ የተነዛው፤ ወልደጊዮርጊስ ፈልገውት ወይም አዘጋጅተውት አለመሆኑን፤ ጃንሆይ ያውቃሉ። ይሁን እንጂ፤ የሰውየው ስም ከአገር ውስጥ አልፎ በውጭውም ዓለም እንደዚህ እየተጋነነ በሚነገርበት ወቅት፤ እሳቸውን ጠቅላይ ሚኒስትር አድርጎ መሾም፤ ሥልጣናቸውን የበለጠ ማጠናከርና አንድ ምቹ ጊዜ ሲያጋጥማቸውም፤ ንጉሠ ነገሥቱን ባዶ እጃቸውን ሊያስቀሯቸው ይችላሉ ተብሎ እንደተሠጋበት የሚታመን ነው።

እንግዲህ፤ ጃንሆይ ጸሐፊ ትዕዛዝን ጠቅላይ ሚኒስትር ማድረግ ያልፈለጉት በእነዚህ በተዘረዘሩት ምክንያቶች መሆኑን ከአመንበት፤ በጸሐፊ ትዕዛዝ በኩል ደግሞ ያለውን ሁኔታ ማየት ይኖርብናል። ጸሐፊ ትዕዛዝ ለአምስት ዓመታት እንደ ጠቅላይ ሚኒስትር ሆነው ሲሠሩ ከቆዩ በኋላ፤ ሹመቱ ስላልተሰጣቸው ከፍ ያለ ቅሬታ ቢያድርባቸው የሚያስደንቅ አይሆንም። ስለዚህም፤ በጃንሆይና በጸሐፊ ትዕዛዝ መካከል ያለው ግንኙነት ወደ ጠብ እያዘነበለ፤ መጀመሪያ መራራትን፤ ቀጥሎ አለመጣጣምን፤ ከዚያም እንደ እሥረኛ ሰው ሆኖ መገመትን አስከተለ።

ጥያቄ፤ ጌታዩ ቢፈቅዱልኝ ከዚሁ ከጸሐፊ ትዕዛዝ ሥልጣን ጋር የተያያዘ በአገራችን አንድ ከልክ ያለፈ የሚወራ ወሬ አለ። ይኸውም ጃንሆይ

የእንግሊዝን አገር በጐበኙበት ጊዜ፤ ጠቅላይ ሚኒስትር ዊንስተን ቸርችል፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ የንጉሠ ነገሥቱን መንግሥት የሚመሩ ትልቁ ባለሥልጣን ናቸው በማለት ለብቻቸው አነጋግሮአቸው ስለነበረ፤ ጃንሆይ በዚህ ተቀይመዋቸዋል እየተባለ ሲወራ ከርሟል። ይህ ታሪክ ለሽረታቸው ተጨማሪ ምክንያት ሆኗል ወይ?

መልስ፤ መጀመሪያ ይህ የተወራው እውነት አይደለም። የፈጠራ ወሬ ነው። ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ምንም ሥልጣን የሚወዱ ቢሆኑ፤ ምንም ወደ ላይ ለማደግ የሚፈልጉ ቢሆኑ፤ ጃንሆይን አልፈው በጀርባ የእንግሊዝን መንግሥት መሪ ለማነጋገር የሚመኙ ወይም የሚሞክሩ ሰው አይደሉም። ቸርችልም ከእሳቸው ጋር ለመነጋገር አልጠየቁም። እርግጥ፤ በዚሁ በሎንዶኑ ጉብኝት ላይ አንድ ልዩ ነገር ታይቶ ብዙ ሰዎች ጃንሆይም ጭምር ሳይደነቁ አልቀሩም። ነገሩ የሆነው በባኪንግሃም ፓላስ ንግሥት ኤልሣቤጥ ለጃንሆይ ክብር ባደረጉት የራት ግብዣ ላይ ነበር።

ጃንሆይ ተከታዮቻቸውን ይዘው ከቤተመንግሥቱ ዋና መግቢያ ላይ ሲደርሱ፤ በፕሮቶኮል ከልዑል መኰንን ቀጥሎ ያሉት ጸሐፊ ትዕዛዝ ነበሩ። ንግሥቲቱና ባለቤታቸው፤ ጃንሆይን እና ልዑል መኰንንን ከተቀበሉ በኋላ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ላይ ሲደርሱ የሰላምታ አሰጣጣቸው የሞቀ መንፈስ ይታይበት ነበር። በተለይ የኤደንብራው መስፍን ስለ እርስም ብዙ አንብቤያለሁ የሚል ቃል ጣል አድርጓል። ከዚያም ከንግሥቲቱ ጥቂት እልፍ ብሎ የቆመው ቸርችል፤ ጸሐፊ ትዕዛዝን እጃቸውን ጨብጦ እያወዛወዘ የጋለ ሰላምታ ሰጣቸው። ወዲያውም፤ " ... ይህንን የስደቱን ዘመን ያሳለፍክበትን አገር እንዴት አገኘኸው? ... " ብሎ ጠየቃቸው። እሳቸውም፤ ልጅ እንዳልካቸው በእንግሊዝኛ እያስተረጐሙላቸው፤ " ... የሰው ልጅ የመከራን ዘመን ያሳለፈበትን አገር እስከ ሕይወቱ ፍጻሜ ሊዘነጋው አይችልም። እኔ ንጉሠ ነገሥቴን እያገለገልኩ በሎንዶን በኖርኩበት በአምስቱ ዓመታት ውስጥ ብዙ ማስታወሻዎች አሉኝ። አሁን ደግሞ በጣም ደስ ያለኝ፤ በዚህ በሰላም ዘመን ተመልሼ መጥቼ ቀድሞ የኖርኩበትን እንደገና የማየት ዕድል ስለአጋጠመኝ ነው ... " አሉት። የእኔ ፕሮቶኮል ከእሳቸው ቀጥሎ ስለነበረ፤ የሰማሁት ይህንን ብቻ ነው። ተጨማሪ ነገር ቢኖር፤ ልጅ እንዳልካቸውን አነጋግረው*። ከዚህ ሌላ እኔ የማስታውሰው፤ የእንግሊዞች ፕሮቶኮል ለጸሐፊ ትዕዛዝ ከፍ ያለ ክብር መስጠቱን ነው። በባኪንግሃም ራት ግብዣ ላይ የተሰጣቸው ወንበር ከንግሥቲቱ እናት (Queen Mother) ቀጥሎ በቀኝ በኩል ነበር። የተሰጣቸውም የኒሻን ሽልማት ለልዑል መኰንን ከተሰጠው ጋር በደረጃ እኩል ስለሆነ፤ አቶ ተፈራወርቅ የጃንሆይ ልዩ ጸሐፊ ለማስለወጥ ሙከራ አድርገው አልቻሉም።

ጥያቄ፤ ንጉሠ ነገሥቱ ጸሐፊ ትዕዛዝን ከመሻራቸው በፊት፤ በመካከላቸው በነበረው ግንኙነት አለመግባባት ወይም አለመጣጣም መፈጠሩ ለተመልካች ግልጽ ኖሮዋል ወይ?

* ከደራሲው፤ ልጅ እንዳልካቸውን አነጋግሬ ጸ.ት አከሊሉ ያሉት ልክ ነው ብለውኛል።

መልስ፤ "ተመልካች" የምትለው ሚኒስትሮቹንና የቤተመንግሥት ባለሟሎችን ከሆነ፤ "አዎን" እልሃለሁ። ... በሁለቱ መካከል የነበረው መግባባት እየቀዘቀዘ መሄዱ ለእኛ በግልጽ የታወቀን፤ ጃንሆይ የአውሮፓን ጉብኝታቸውን ፈጽመው አዲስ አበባ እንደተመለሱ ነው። አቶ መኰንንም እንደነገረኝ፤ ስለ ጃንሆይ የሥራ አመራር ጉዳይ ሁለቱ ሲወያዩ፤ ሳይግባቡ የቀሩትና ከመለያየት የደረሱት፤ ጃንሆይ ከአውሮፓ አዲስ አበባ በገቡበት ዕለት ማታ ነው።

እኔና እኔን የመሳሰልነው ሰዎች እንዳስተዋልነው፤ ለውጥ ያሳዩት ከጃንሆይ ይልቅ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ነበሩ። ድሮ፤ ጃንሆይ የማይሆን ትዕዛዝ ሲሰጡ፤ ወይም አስፈላጊ ያልሆነ ውሳኔ ሲያደርጉ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ለጊዜው የጃንሆይን ውሳኔ በአክብሮት የተቀበሉ ያስመስሉና፤ ሰው በሌለበት ሰዓት በቀይታ ገብተው ክፋውንና ደጉን እየለዩ በማስረዳት ሐሳባቸውን ያስለውጧቸው ነበር። ወደ መጨረሻው ጊዜ ግን፤ ሰው ቢኖር ባይኖር፤ ጃንሆይ የተናገሩትን ወይም ያዘዙትን ጸሐፊ ትዕዛዝ መቀበል ካልፈለጉ፤ እዚያው ላይ ይቃወማሉ። አንዳንድ ጊዜም፤ ይህ የተወሰነው ልክ አይደለም ብለው ክርክሩን ያጠነክራሉ። በዚህ ጊዜ ጃንሆይ፤ በጸሐፊ ትዕዛዛቸው ላይ ምን ያህል ቅሬታ እንደተሰማቸው የሚታወቅባቸው፤ ወደ ቁጣ ሲያዘነብሉ ነበር። ይህ በሁለቱ መካከል በአምሳለ ገነት ጽሕፈት ቤት የሚታየው የአለመጣጣም ሁኔታ ለምን ያህል ጊዜ እንደሚቀጥል ባናውቀውም፤ በመጨረሻው የጃንሆይንና የወልደጊዮርጊስን መለያየት እንደሚያስከትል ለብዙዎቻችን ታይቶን ነበር። ጸሐፊ ትዕዛዝም ይህ እንደሚደርስባቸው የሚያውቁ ናቸው። ይህን በመሰለ ሁኔታ አንድ የነገሩኝን ነገር ልገልጽልህ እፈልጋለሁ።

ጃንሆይ ከአውሮፓ ጉብኝታቸው ከተመለሱ በኋላ፤ ስለ ኦጋዴን ግዛታችን ጉዳይ፤ ከእንግሊዝ መንግሥት ጋር የጀመርነውን ንግግር ለመቀጠል ወደ ሎንዶን መሄድ ነበረብኝ። በምንሄድበት ቀን፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ምንም እንኳ በእኔ ላይ የመቀየም መንፈስ ሲያሳዩኝ ቢሰነብቱም፤ ድሮ እንደሚያደርጉት ሊሸኙኝ አውሮፕላን ጣቢያ መጥተው ነበር። በዚያን ጊዜም ይህንን ያስለመዱኝን መለወጥ አልፈለጉም። የመሳፈሪያው ሰዓት ደርሶ ስሰናበታቸው፤ እጄን ይዘው፤ "አክሊሉ! ስትመለስ የምታመጣልኝ አንድ መጽሐፍ አለ " አሉኝ። ምንድን ነው? ስላቸው፤ በቅርቡ በፈረንሣዊኛ ተተርጉሞ የወጣውን የታወቀውን የፖለቲካ መሪ የጀርመናዊውን የኦቶ ቢዝማርክን (Otto Bismarck) ታሪክ ነው አሉኝ። እኔም ትንሽ መቀለድ አማረኝና፤ " ... ቢዝማርክ እኮ ያልተሳካለት የፖለቲካ ሰው ነው። ከንጉሠ ነገሥት ቀዳማዊ ጊዮም ጋር በሙሉ ሥልጣን እንደልቡ ለብዙ ዓመታት ከሠራ በኋላ፤ አዲሱ ንጉሠ ነገሥት ዳግማዊ ጊዮም ሲተካ፤ ከሥልጣን ተባርሮ የመጨረሻ ዘመኑን በትካዜ ያሳለፈ ስለሆነ፤ ምሳሌነቱ ጠቃሚ አይደለም ... " አልኳቸው። የእኔ የተንኮል አነጋገር ወዲያውኑ ስለገባቸው፤ " ... መቼም ቢዝማርክ ያልተሳካለት የቀዳማዊ ጊዮምን ዘመን በደህና ከፈጸመ በኋላ፤ ወደ ዳግማዊ ጊዮም ዘመነ መንግሥት ሲሸጋገር ነው። እኔ ግን፤ ወደ ዳግማዊው ሳልሻወር በቀዳማዊው ዘመን የምሰናበት ሰው ስለሆንኩ፤ አንተ እንደፈራኸው የቢዝማርክ ምሳሌ አያስጋኝም ... " ብለውኝ፤ በጣም

ተሳስቀን ተለያየን። እንግዲህ ከዚህ ምሥጢራዊ አነጋገር ለመረዳት የሚቻለው፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ በቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ዘመን የፖለቲካ ሥልጣናቸውን ጨርሰው እንደሚሰናበቱ፣ የሚያውቁ መሆናቸውን ነው።

ብዙ ጊዜ ደጋግሜ እንደነገርኩህ፣ እኔ የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን የተፈጥሮ ብልህነትና ጠንካራ ሠራተኛነት አደንቃለሁ። ሆኖም ጉዳት ላይ የሚጥል ጠባይ ያየሁባቸው፣ በራሳቸው ከመተማመን የተነሣ፣ ለጠላቶቻቸው ምንም ሥጋት የሌላቸው መሆናቸው ነው። በኤክስፔሪያንስ እንደምናየው፣ ብዙዎቹ የፖለቲካ ሰዎች ባለጋራዎቻቸውን አይንቁም። ስለዚህም፣ ድክመታቸውን እያጠኑ፣ ምቹ ጊዜ ሲያጋጥማቸው እርምጃ በመውሰድ ያጠቃሉ። ጸሐፊ ትዕዛዝ ግን የዚህ ዓይነት ዘዴ የላቸውም። እሳቸው የሚያምኑት ጠላቶቻቸውን ፊት ለፊት ገጥሞ ድራሹን ማጥፋት ነው። የዚህ ዓይነቱም የአሠራር ስልት፣ አንዳንድ ጊዜ ውጤት ቢሰጥም፣ አንዳንድ ጊዜ ደግሞ እንደሚከሽፍ መታሰብ ነበረበት። በእኔ አስተያየት በጸሐፊ ትዕዛዝ ላይ በመጨረሻው የደረሰባቸው፣ ጠላቶቻቸውን በመናቅና በጃንሆይም ላይ ሙሉ ዕምነት በማሳደር ነው። ጃንሆይ በፊታቸው ላይ ጥቁር ዳመና ሲጥሉባቸው፣ አንዳንድ ሰዎች እንደሚያደርጉት ተለማምጦ ዳመናውን በመግፈፍ ፋንታ፣ በዚያ በመከራው ዘመን ያልተለዩኋቸውና ቀጥሎም አዲሲቷ ኢትዮጵያ ስትገነባ አብሬአቸው የተጋፈጥኩ ስለሆነ፣ ዛሬ እኔን ትተው ብቻቸውን ሊቆሙ አይችሉም የሚል ሐሳብ ሳያድርባቸው አልቀረም። ከመሻራቸው በፊት አንዳንድ ጊዜ በቀልድ ሲናገሩ እንደሰማኋቸው፣ " ... የተጠነሰሰልኝ ጥንስስ ጠላ ሆኖ ለመቅረብ የሚችለው መቼ እንደሆነ ባላውቀውም፣ ድሮ ሆስፒታል የሠራሁ በመሆኔ፣ የጤና ጥበቃ ሚኒስትርነት ሳይታሰብልኝ አይቀርም ... " ይሉ ነበር። በዚህ አነጋገር ቀደም ብዬ እንደጠቀስኩት፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወደ እሩሲ መሄዳቸውን ነው እንጂ ያላወቁት፣ ከነበሩበት ሥልጣን እንደሚነሱ እርግጠኛ መሆናቸው አያጠራጥርም። ... መቼም ብዙ ጊዜ የታሰበበትና የተለየ ጥረት የተደረገበት ጉዳይ ሰዓቱን ጠብቆ መፈጸሙ የማይቀር ስለሆነ፣ ያቺ የሚያዝያ 17 ሰኞ እንደምንም ደርሳ፣ ንጉሠ ነገሥቱ የሽረት በንባቸውን ሲያፈነዱ፣ አጅሬ ወልደጊዮርጊስም ሳይዛነፉ እንደድሮአቸው ቀጥ ብለው፣ የማክበር ሰላምታ ሰጥተው ወጡ። አንድ ወዳጄ ስሙን መናገር የማልፈልገው፣ በጸሐፊ ትዕዛዝ ሽረት ጊዜ የተናገረውን መጥቀስ እፈልጋለሁ። " ... በጃንሆይና በጸሐፊ ትዕዛዝ መካከል የተፈጠረው ጠብ፣ ወልደጊዮርጊስ ለምን ጠቅላይ ሚኒስትር አልሆንም? በማለት ሲሆን፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ደግሞ፣ እረ ! ሥልጣኔን ልትቀማኝ? ... ሞኝህን ፈልግ ... ብለው ነው። እኔ ብዙ ጊዜ የጃንሆይን ውሣኔና አሠራር አልቀበለውም። ሆኖም፣ ወልደጊዮርጊስን ጠቅላይ ሚኒስትር አለማድረጋቸው፣ ጥንቁቅነታቸውን የሚያሳይ ስለሆነ፣ እደግፋቸዋለሁ። ጃንሆይ ቢሾሟቸው ኖሮ ለውጡን በአጭር ጊዜ ውስጥ ያገኙት ነበር። " ... እኔ ጠቅላይ ሚኒስትር ሆኜ የመንግሥቱ መሪ እሆናለሁ። እርስዎ ደግሞ፣ የኢትዮጵያና የሕዝቦቿ አባት ሆነው፣ ታሪኳንና ባህሏን ለመገንባት፣ በዓለም ላይ እየተዘዋወሩ ያስተዋውቋታል ... " ብለው፣ እጃቸውን አሥረው ያለአንዳች ሥልጣን ያስቀምጧቸው ነበር ... " አለኝ። መቼም የየሰዉ አስተያየት ዓይነቱ ብዙ ነው። የሆነ ሆኖ፣

በዚያም ተባለ በዚህ፤ ወልደጊዮርጊስ ርቀው ሄደዋል። በተዓምር አንድ ቀን ወደ ሥልጣናቸው ካልተመለሱ በስተቀር፤ .....

ጥያቄ፤ ለመሆኑ ጸሐፊ ትዕዛዝ ይመለሳሉ ተብሎ ይታሰባል?

መልስ፤ በፖለቲካ ዓለም ብዙ ጊዜ የሚደርሰው ያልታሰበው ነው። ሆኖም ቢታሰብም ባይታሰብም አንድ ቀን ያልታሰበው ብቅ ቢል አያስደንቅም።

ጥያቄ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ በተሻሩበት ዕለት እናንተ "ሀብተወልድ ወንድማማቾች" ለወጉ እቤታቸው አልሄዳችሁም ወይ? ...

መልስ፤ አዋጁ በተነገረ ማግሥት እኔና አካለወርቅ ጸሐፊ ትዕዛዝ ቤት ሄደን ነበር። አሁን ለጊዜው ወጣ ብለዋል፤ የሉም ተብለን ከበር ተመለስን። ከዚያም ጥቂት ቀን በኋላ እኔ ግቢ አግኝቻቸው፤ ከአካለወርቅ ጋር መጥተን ሳናገኝዎ ተመለስን አልኳቸው። አዎን! ሰምቻለሁ። ምን አደከማችሁ? ብለውኝ ሄዱ። ንግግሩን መቀጠል አልፈለጉም ነበር። እንደሰማሁት፤ ከካቢኔ ሚኒስትሮች መካከል ከባላምባራስ ማሕተመሥላሴ የእርሻ ሚኒስትር በስተቀር ሌላ ጸሐፊ ትዕዛዝ ቤት የሄደ የለም።

ጥያቄ፤ ብዙ ሰዎች ሳይሄዱ የቀሩት፤ ጃንሆይ ለምን ሄዳችሁ? ይሉናል ብለው በመፍራት ይሆን? ...

መልስ፤ ብዙ ሰዎች ለምን እንዳልሄዱ ምክንያቱን እኔ አይደለሁም የምናገረው። ጠያይቆ መድረስ ያንተ ፋንታ ነው። እንደነገርኩህ እኔ ሄጃለሁ። ይልቅ እቤታቸው ባገኛቸው ኖሮ፤ ምን ልላቸው እንዳሰብኩ እነግርሃለሁ። " ... ጸሐፊ ትዕዛዝ! እርስዎ ራስዎ ጃንሆይ እኛን እያከረሩ በሚቆጡን ጊዜ፤ እንግዲህ ይሽሩናል እያልን ስንጠባበቅ፤ እርስዎ የሚያጽናኑን፤ ፀሐይና ንጉሥ ተለዋዋጭ ነው። ፀሐይ ሲሞቅ ያቃጥላል። ንጉሥም ሲቆጣ ይቀጣል። መድኃኒቱ ትዕግሥት ነው ... " እያሉ ይመክሩን ነበር። ዛሬ በእርስዎ ላይ የደረሰውን፤ እኔ የምመለከተው በዚህ መልክ ስለሆነ፤ ደህናው ቀን እስከሚመለስ ድረስ፤ እግዚአብሔር ትዕግሥትዎን ያጠንክርልዎ ብዬ መልካም ምኞቴን ለመግለጽ ነው የመጣሁት እላቸው ነበር። ባለመታደል አላገኘኋቸውም። ለመናገር ያቀድኩትም ሐሳብ እንዲሁ ሐሳብ ሆኖ ቀርቷል።

ጥያቄ፤ ከካቢኔ ሚኒስትሮች ውስጥ ጃንሆይ በጸሐፊ ትዕዛዝ ላይ የወሰዱትን እርምጃ የሚደግፉት ይበዛሉ? ወይስ ቅጣቱ በዝቶባቸዋል ብለው የሚያዝኑት?

መልስ፤ ለዚህ ጥያቄ አንተው ራስህ መርምረህ ብትደርስበት ይሻላል። እኔ የጸሐፊ ትዕዛዝን ደጋፊዎችና ተቃዋሚዎች እየለየሁ ሒሣብ አላወጣሁም። ግን አንድ ነገር በትክክል መገንዘብ አለብህ። ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን ጃንሆይ የሻሯቸው፤ በአገር ላይ በደል አድርሰው፤ ወይም ደግሞ ለንጉሠ ነገሥቱ ታማኝነታቸውን አጓድለው አይደለም። የተሻሩት፤ በፖለቲካ ሚዛን በተሰጠ ፍርድ ነው። ትንሽ ግልጥ ለመሆን፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ የሥልጣን አጠቃቀማቸውና አያያዛቸው፤ የሚያሠጋ ነው ተብሎ ነው።

ስለዚህ፣ ከካቢኔ ሚኒስትሮች መካከል የሰውየው ወዳጆች የሆኑት ሲያዝኑ፣ ተቃዋሚዎች ነን የሚሉት ደግሞ መደሰታቸው አይጠረጠርም። እኔ ጸሐፊ ትዕዛዝ ባያምኑበትም፣ ካዘኑት ውስጥ ነበርኩ። ያዘንኩትም፣ ለምን ከጽሕፈት ሚኒስቴር ተነሡ? ብዬ አይደለም። ይፍጠን ወይም ይዘግይ እንጂ፣ ከዚያ ቦታ አንድ ቀን መነሣታቸው የሚቀር አልነበረም። ነገር ግን ያንን ሁሉ ሥልጣን የነበራቸውንና ከፍተኛም አገልግሎት ያበረከቱትን ሰው፣ እስከዚህ ዝቅ አድርጐ መሻር የሚገባ አይደለም ብዬ ነው። ጃንሆይ በዚያን ጊዜ እኔን እንደ ትልልቆቹ ሰዎች ቆጥረው አማክረውኝ ቢሆን ኖሮ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝን ለማዛወር ሁለት ቦታዎችን አቀርብላቸው ነበር።

1ኛ/ በኤርትራ የግርማዊነታቸው እንደራሴ ቢያደርጓቸው፣ የኤርትራን ጉዳይና የኤርትራውያን ወንድሞቻችንን ፍላጐት ደህና አድርገው ስለሚያውቁ፣ ጥሩ ውጤት ይሰጡ ነበር።

2ኛ/ ጃንሆይ የፈለጉት ለጊዜው እሳቸውን ከአጠገባቸው ማራቅ ከሆነ፣ በፓሪስ አምባሳደር አድርገው ቢልኳቸው የተገባ ይሆን ነበር። ጸሐፊ ትዕዛዝም ከእነዚህ ከሁለቱ አንዱን ሹመዋቸው ቢሆን ኖሮ፣ በተለይም በፓሪስ አምባሳደርነትን ያለ አንዳች ቅሬታ ይቀበሉ ነበር። ለማናቸውም፣ እኔ አልተጠየቅኩም።

ጥያቄ፣ ጌታዬ ቢፈቅዱልኝ፣ አሁን የማቀርበው ጥያቄ የመጨረሻው ነው። ጃንሆይ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን በመሻር ምን ጠቀማቸው? በሌላስ በኩል ምን ጐዳቸው?

መልስ፣ በእኔ አስተያየት፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን ከሥልጣን በማውረድ፣ ጃንሆይ ከመጋረጃ ወጥተው በማናቸውም ሥራ ውስጥ ጠልቀው ገብተዋል። ጸሐፊ ትዕዛዝ በነበሩ ጊዜ፣ ጃንሆይ በየዕለቱ የሚሠሩትንና የሚወስኑትን በየጉዳዩ እየለዩ ስለሚያዘጋጁላቸው፣ ፕሮግራሙን እየተከተሉ ከመፈጸም በስተቀር ሌላ ኃላፊነት አልነበረባቸውም። ከዚህም በቀር ያልተጻፈ ዲስኩር አያደርጉም። ያልተጠና ጉዳይ አይወስኑም። በእኔ ግምት በዚህ ረገድ ጃንሆይ ተጐድተዋል። ጸሐፊ ትዕዛዝ ከሄዱ በኋላ፣ ሚኒስትር ሆነ፣ ጠቅላይ ገዥ ወይም የድርጅት መሪ፣ በአምሳለ ገነት ጽሕፈት ቤት ጉዳዩን ሲያቀርብ፣ ጃንሆይ አዳምጠው የመሰላቸውን ውሳኔ ሲሰጡ፣ አዲሱ የጽሕፈት ሚኒስትሩም በጃንሆይ የተወሰነውን ቃል በቃል ጽፎ ማዘዣውን ከማስተላለፍ በስተቀር፣ የተፈቀደውን ጉዳይ ዝርዝሩን በጥልቀት ስለማይከታተል፣ ብዙ ነገሮች እየተዘበራረቁ የተሠሩትንና ያልተሠሩትን መለየት ሲያቅት አይቻለሁ። ይኸ፣ በአንድ በጽሕፈት ሚኒስቴር ብቻ ያለው ነው። ሌላው ደግሞ የጸሐፊ ትዕዛዝ አለመኖር ትልቅ ክፍት ቦታ የተወው፣ በጃንሆይ ሰብሳቢነት በሚደረጉት ታላላቅ ጉባኤዎች ላይ ነው። ጸሐፊ ትዕዛዝ በነበሩ ጊዜ፣

1ኛ/ በስብሰባው ላይ ንግግር የሚደረጉባቸው ጉዳዮች በፕሮግራም ተዘርዝረው ለተካፋዮቹ ይሰጣሉ።

2ኛ/ ጃንሆይ ጉባኤውን ሲከፍቱ የሚሰጡትን መግለጫ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ማብራሪያ ይሰጣሉ።

3ኛ/ በስብሰባው ላይ ንግግር የተደረጉባቸው ጉዳዮች ምን ዓይነት ውሳኔ እንደተሰጠባቸው፣ ፕሮሲቬርባል ተዘጋጅቶ ለተካፈሉት ሰዎች ይላካል።

ይህንን ሁሉ ሥርዓት አስይዘው የሚያዘጋጁትና የሚያስፈጽሙት፣ ራሳቸው ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ነበሩ።

ጸሐፊ ትዕዛዝ ከሄዱ በኋላ፣ በጃንሆይ ቢሮ የሚደረገው ስብሰባ ሁሉ ምን ያህል እንደተዘበራረቀ ይታይ ነበር።

መጀመሪያ፣ ስብሰባ የሚደረገው በማናቸውም ሰዓት ነው።
ሁለተኛ፣ አጀንዳው የሚታወቀው ስብሰባው ሲከፈት ነው።
ሦስተኛ፣ በስብሰባው ላይ ተካፋይ የሆኑት ሰዎች የሚሰጡት ሐሳብ ባዳመጡት ጉዳይ ላይ ብቻ ስለሆነ፣ የተጠና ወይም የበሰለ አስተያየት ማቅረብ አይችሉም።
አራተኛ፣ የስብሰባው ቃለ ጉባኤ በሚገባ ተይዞ፣ ከነውሳኔው ለአባሉቹ አይላክም።

በዚህ በጃንሆይ ቢሮ ስለሚደረጉት ታላላቅ ጉባኤዎች ጉዳይ፣ (የዘውድ ምክር ቤት አባሎችና የካቢኔ ሚኒስትሮች) አንድ ጊዜ ራስ ካሣ ተናገሩ ተብሎ የሰማሁት፣ ዘወትር ሲያስደንቀኝ ይኖራል። ጉዳዩ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን የሚመለከት ነው። " ... ኧረ ይኸ እኛን የማይወደን እኛም የማይናፍቀን ሰው ከሄደ በኋላ፣ በሥራው አጉድሎናል ብለን ብንናገር፣ ተተኪዎቹን ያተጋልን ይሆን? ... " አሉ ይባላል።

ጥያቄ፣ ጌታዬ በጣም ይቅርታ እንዲያደርጉልኝ እየለመንኩ፣ ከዚህ በፊት ያቀረብኩት ጥያቄ የመጨረሻዬ ነው ብዬ ነበር። አሁን ደግሞ አንድ ሌላ ነገር ተገለጠልኝ።

መልስ፣ ቀጥል .....

ጥያቄ፣ የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ጉዳይ ከተዘጋ ይኸው አሥራ አምስት ዓመታት አልፏል። በእነዚህ ዘመን ውስጥ እስከ ዛሬ ድረስ፣ ጃንሆይ እንደ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ያቀረቡት፣ እምነውም ሥልጣን የሰጡት፣ ለማን ነው? ቢባል፣ ማንን መጥቀስ ይቻላል?

መልስ፣ ማ ን ን ም !

ጥያቄ፣ ብዙ ሰዎች የሚያወሩት አቶ መኮንን ጸሐፊ ትዕዛዝን ካሻሩ በኋላ ሥልጣኑን የወረሱት እሳቸው ናቸው እያሉ ነው። ይህ እውነት ነው ወይ?

መልስ፤ ውሸት! ... ከዚህ በፊት እኔ የማምንበትን ነግሬህ ነበር። ግልጽ ካልሆነልህ እንደገና እደግምልሃለሁ። ጃንሆይ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን የሻሯቸው፤ ለመኰንን ሀብተወልድ ሲሉ፤ ወይም በእሱ ሐሳብ ተመርተው አይደለም። ጃንሆይ ጸሐፊ ትዕዛዝን ከዚያ ከነበሩበት ከትልቅ ደረጃ እንስተው የጣሏቸው፤ "የሥልጣን አያያዛቸውና አረማመዳቸው የሚያሠጋ ሆኗል ... " ተብሎ በራሳቸውና በመላው ንጉሣዊ ቤተሰባቸው የታመነበት ጉዳይ በመሆኑ ነው። ይህንንም ብዙውን ሰው ያስደነገጠ እርምጃ ጃንሆይ ከመውሰዳቸው በፊት፤ ንጉሣውያን ቤተሰብ፤ መሳፍንትና መኳንንት፤ ጳጳሱም ጭምር የተካፈሉበት፤ ብዙ ምርምር፤ እና ብዙ ጥናት ተደርጉበታል። ስለዚህ፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ የተሻሩት በአንድ ሰው ኃይል በመኰንን ሀብተወልድ ነው ብለው የሚያወሩት ሰዎች፤ የወልደጊዮርጊስን የፖለቲካ ክብርና ትልቅነት ምን ያህል እንደሚቀንሱት ያልተረዱት ብቻ ናቸው። ጸሐፊ ትዕዛዝ ከሥልጣን ከወረዱ በኋላ ደግሞ፤ የእሳቸውን ቦታ የወረሰው አቶ መኰንን አይደለም። ከእሳቸው ሽረት በኋላ፤ አቶ መኰንን ቀድሞ ከነበረው የአንድ ሚሊ ሜትር ሥልጣን አልጨመረም። ስለዚህ ወልደጊዮርጊስን የሻሯቸው ራሳቸው ጃንሆይ ሲሆኑ፤ ሥልጣኑንም መልሰው የያዙት ራሳቸው ጃንሆይ ናቸው። እኔ ይህንን ስናገር፤ አባቴ ወንድሜ የሆነው መኰንን ሀብተወልድ፤ ለወልደጊዮርጊስ ሽረት ከጃንሆይ ጋር አልቆመም፤ ከጃንሆይ ጋር አልሠራም ለማለት አይደለም። የታዘዘውን ሁሉ ፈጽሟል። ይህንንም ሲያደርግ፤ ባለው መሠረታዊ አቋም ላይ ፀንቶ ነው። ይኸውም፤ "ለኢትዮጵያ ያሏት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ብቻ ናቸው" ብሎ ስለሚያምን፤ እሳቸው የሚፈልጉትንና የሚወዱትን ከግቡ ለማድረስ በሚገባ ሠርቷል። ይህንንም የማይነቃነቅ ዕምነቱን ለማንም ደብቆት አያውቅም። " ... እንኳንስ ወዳጆቼ፤ ልጆቼም ሆኑ ወንድሞቼ፤ ከጃንሆይ አይበልጡብኝም ... " ብሏል። ስለዚህ፤ አቶ መኰንን ሀብተወልድ ለጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ሽረት የታዘዘውን በመፈጸሙ፤ እሱ ቦታ ሆነው ችግሩን ለተረዱለት ሆነ ወይም ደግሞ መረዳት ባለመፈለግ ለሚያወግዙት ሰዎች፤ የማቀርበው የተለየ ማስረጃ የለኝም።

ከዚህ በላይ የቀረበውን አንባቢዎች እንደተመለከቱት፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ከዚያ ከትልቁ ሥልጣናቸው የተሻሩት፤ በጓደኛው በአቶ መኰንን "ባላጋራነት" ነው ተብሎ በአፍ ታሪክ በሰፊው የሚወራው ሁሉ ትክክል አይደለም ሲሉ፤ አክሊሉ ሀብተወልድ የሰጡትን ዝርዝር አስተያየት በጥልቀት መረዳት ያስፈልጋል። የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወገኖችም ቢሆኑ፤ አጅሬን ከዚያ ሁሉ ሥልጣን ለማንሳትና ወደ ገጠር አስተዳደር ለማዛወር የተወሰደው እርምጃ፤ በአንድ ሰው ምክንያት ሳይሆን፤ በንጉሠ ነገሥቱ ብርቱ ፍላጎትና ውሳኔ መሆኑን ለማመን ይቸገራሉ ተብሎ አይታሰብም። አክሊሉ ሀብተወልድ እንዳሉት፤ ይህ ሁሉ የደረሰው በአቶ መኰንን ጥረት ነው ብሎ የታሪኩን ምዕራፍ መዝጋት፤ ወልደጊዮርጊስ የነበራቸውን ከፍተኛ ቦታና የሥልጣን ኃይል ምን ያህል እንደሚያቃልለው መገንዘብ ያስፈልጋል።

ማንም ሰው እንደሚያውቀው፣ በፖለቲካ ዓለም ውስጥ አንድ ችግር ሲደርስ፣ አባት ልጁን፣ ልጅ አባቱን፣ ወንድም ወንድሙን፣ ጓደኛ ጓደኛውን ጥሎ ዘወር እንደሚልና የራሱን ጥቅም እንደሚጠብቅ፣ በብዙ አገሮች ታሪክ ተደጋግሞ የደረሰና የታየ ነው። ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ወልደጊዮርጊስን ከትልቁ ሥልጣናቸው ለመሻርና ከአጠገባቸው ለማራቅ ቆርጠው ሲነሱ፣ መኰንን ሀብተወልድም ጃንሆይን ትተው ከተጠቂው ጓደኛቸው ጋር መቆም ነበረባቸው ብሎ ፍርድ የሚሰጥ የሚኖር አይመስልም። ስለ ወልደጊዮርጊስ ጉዳይ በግርማዊት ቪላ በተደረገው ስብሰባ፣ አቶ መኰንን በጓደኛቸው ላይ የሚወሰደው እርምጃ መጠንከር የለበትም ወይም መሻሻል ይኖርበታል ብለው አልተሟገቱም። ሆኖም ስለ ጸሐፊ ትዕዛዝ ትክክል ያልሆነ ክስ እንዲቀርብ አለመስማማታቸውን በሚገባ ተናግረዋል። ያውም ራስ ካሣ ሁለታችሁም በአንድነት የእኛን የመሳፍንቱን ቤተሰብ ትቃወሙ አልነበረም? በማለት እንደዚያ በንግግር ሲያጠቋቸው፣ " ... <u>በአንዳንድ አገሮች ላይ እንደደረሰው፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ በጃንሆይ መንግሥት ላይ ለመሸፈት ያሰባል ወይም ይመኛል ብዬ አላምንም</u> ... " ሲሉ መኰንን ሀብተወልድ የሰጡት ምሥክርነት በቀላሉ የሚገመት አይሆንም። ይህም ሲባል፣ አቶ መኰንን ለጸሐፊ ትዕዛዝ ሽረት፣ ከታላላቆቹ መሳፍንትና መኳንንት ጋር የግርማዊት ቪላ ስብሰባ ተካፋይነታቸውንና የንጉሠ ነገሥቱንም ፍላጐት በትክክል ፈጻሚነታቸውን ለመሸፈን አይደለም። ገና ከጠዋቱ በቆሙበት ዕምነት፣ " ... እንኳንስ ጓደኞቼ፣ ልጆቼም ሆኑ ወንድሞቼ፣ ከቀዳማዊ ኃይለሥላሴ አይበልጡብኝም ... " ሲሉ የተናገሩትን ማስታወስ ያስፈልጋል። እንደተመለከትነውም ከሆነ፣ መኰንን ሀብተወልድ በወልደጊዮርጊስ ጉዳይ የፈጸሙት ይህንኑ መሠረታዊ ዕምነታቸውን ተከትለው ነው።

## ከደራሲው

ከዚህ በላይ ያቀረብኩት የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መንግሥት ታሪክ የመጀመሪያው ክፍል የሚቆመው፣ እዚህ ምዕራፍ ላይ ነው። ከጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ከሥልጣን መልቀቅ በኋላ፣ እስከ "ደርግ" አመጣጥና የንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት ፍጻሜ እስከሆነበት ጊዜ ድረስ ያለው ታሪክ፣ በሁለተኛው ክፍል የሚቀርብ መሆኑን ለአንባቢዎቼ በትሕትና እገልጻለሁ።

ዘውዴ ረታ

# የመጽሐፉን ዓቢይ ጉዳዮች ማብራሪያና

# ዋቢ መረጃዎች

እንደ ኢት.አቆ. ከ1923 እስከ 1948 ዓ.ም ድረስ ያለውን የቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴን መንግሥት ታሪክ ጽፎ ለማሳተም፣ ደራሲው ረጅም ጊዜ እንደወሰደበት ቀደም ሲል በመግቢያው ላይ ለአንባቢዎቹ የገለጸ መሆኑ ይታወሳል። የዚህም ዋናው ምክንያት፣ በእነዚህ በተጠቀሱት የሀያ አምስት ዓመታት ውስጥ፣ በኢትዮጵያ የተከናወኑት ታሪካዊ ድርጊቶች ከብዛታቸው በላይ እጅግ የተወሳሰቡና ለአጻጻፍም ሆነ ለአገላለጽ ምቹ ባለመሆናቸው እንደሆነ ደራሲው አስረድቷል።

በስምንት ዋና ዋና ክፍሎች ደልድሎ ደራሲው ጽፎ ያቀረበውን ታሪክ፣ መረጃዎቹን ለመሰብሰብ ያደረገውን ጥረት እንደሚከተለው በዝርዝር ይገልጻል።

## አንደኛው ክፍል፣

ተፈሪ መኰንን ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ተብለው እንደ ኢት.አቆ. ጥቅምት 23 ቀን 1923 ዓ.ም በመናገሻ ቅዱስ ጊዮርጊስ ቤተክርስቲያን ሲነግሡ፣ የተከናወነው ዝርዝር የንግሥ በዓል በቤተመንግሥቱ ዜና መዋዕል በሰፊው ተጽፎ ይገኛል። (ጽሕፈት ሚኒስቴር አርሺቭ)

በቀ.ኃ.ሥ ንግሥ በዓል ተካፋይ እንዲሆኑ የተጋበዙት የአራቱ ታላላቅ መንግሥታት፣ የአሜሪካና የእንግሊዝ፣ የፈረንሣይና የጣልያን እንደራሴዎች ወደየአገራቸው ሲመለሱ፣ ስለተደረገላቸው መስተንግዶና ስለ ኢትዮጵያ ሁኔታ የቃረሟቸውን አስተያየቶች ለየመንግሥታቶቻቸው ያቀረቧቸው ራፖሮች ለኢትዮጵያ ነፃነት ዋስትና የሚሰጡ አልነበሩም። ለእነዚህም መረጃዎች፣

1. በዋሽንግተን - "National Archives Index Bureau 884.001/198
2. በሎንዶን - Public Record Office FO 371/15 389
3. በፓሪስ - Ministere Des Affaires Etrangeres (Dossier Afrique) « Ethiopie »
4. በሮም - Palazzo Farnesina Archivo Diplomatico e Storico (Etiopia) ያሉት ሰነዶች ያስረዳሉ።

በዚሁ በአንደኛው ክፍል ውስጥ በኢትዮጵያ ታሪክ ለመጀመሪያ ጊዜ የቆመው ሕገ መንግሥት፣ በምን አኳኋን እንደተዘጋጀ፣ ቀ.ኃ.ሥ ሕይወቱና

የኢትዮጵያ እርምጃ በተባለው መጽሐፋቸው ውስጥ ከገጽ 147 እስከ 167 ድረስ ገልጸውታል። ሆኖም በአዘጋጁ ኮሚቴ አባሎች መካከል፣ በተለይም በራስ ካሣና በበጅሮንድ ተክለሐዋርያት መካከል ስለተደረገው የሐሳብ መለዋወጥና ክርክር፣ የጽሕፈት ሚኒስቴር ባለሥልጣኖች አቶ ተክለማርቆስና አቶ ገብረወልድ እንግዳወርቅ የያዙትን ዝርዝር ቃለ ጉባኤ መመልከት ያስፈልጋል። (የጽሕፈት ሚኒስቴር ዶሴ ሐምሌ 1923 ዓ.ም)

በዚሁ በአንደኛው ክፍል በምዕራፍ 4 ላይ "ሙሶሊኒ" ከምን ተነስቶ ጣልያንን ለመምራት እንደበቃ ደራሲው በሰፊው የጻፈው፣ ከሠላሳ ዓመታት በላይ ሮም በኖረበት ዘመን በልዩ ልዩ ጸሐፊዎች የቀረቡትን ሰነዶች በማጥናት ነው። ከእነዚህም ውስጥ "Max Gallo" የተባለው ፈረንሣዊ ደራሲ "L'Italie De Mussolini" በሚል ርዕስ የጻፈው መጽሐፍ የተሟላ ሰነዶችን የያዘ መሆኑን ደራሲው ለተመራማሪዎች ይጠቁማል።

## ሁለተኛው ክፍል፤

"ጥቁር ደመና በኢትዮጵያ ፀሐይ" በሚል ርዕስ የተከፈተው ሁለተኛው ክፍል፣ ሰባት ምዕራፎችን ይዞ ቀርቧል። በእነዚህም ምዕራፎች ውስጥ የተተነተኑት ታሪካዊ ሰነዶች፣ ሙሶሊኒ የአድዋን ብድር መመለስ አለብኝ ብሎ ኢትዮጵያን በጦር ለመውረር ያደረጋቸውን ዝግጅቶች፣ ከወልወል ግጭት ጀምሮ እስከ መንግሥታት ማኅበር ሽምግልና ድረስ የነበረውን ሁኔታ በሰፊው የሚያስረዳ ነው።

ሙሶሊኒ ኢትዮጵያን በጦር ለመውረር ቆርጦ ሲዘጋጅ፣ ጦርነቱን ከመክፈቱ በፊት በጣም የደከመበትና ያሰበበት፣ ኢትዮጵያ ፍጹም ፊውዳል በሆነ ሥርዓት እየተዳደረች በሕዝቦቿ ላይ የአረመኔ ተግባር በመፈጸም ላይ ትገኛለች የሚል የፕሮፓጋንዳ ክስ በማቅረብ፣ ከመንግሥታት ማኅበር አባልነቷ እንድትወገድ ለማድረግ ነበር። ነገር ግን የኢትዮጵያ መልዕክተኛ በጅሮንድ ተክለሐዋርያት "እናንተው ፍረዱ" በሚል ርዕስ ከፋሽስቱ መልዕክተኛ ከባሮን አሎዊዚ ጋር ያደረጉት ሙግት፣ አብዛኞዎቹን የመንግሥታት ማኅበር እንደራሴዎች ስለማረከ፣ የሙሶሊኒ ክስ በገኔቭ ሸንጎ ላይ ውድቅ ሆነ።

<u>በዚህ በሁለተኛው</u> የታሪክ ክፍል ውስጥ፣

- የወልወል ግጭት እንዴት እንደተፈጠረ፣
- በኢትዮጵያ ጉዳይ የፈረንሣይ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ፒየር ላቫልና የፋሽስቱ መሪ ቤኒቶ ሙሶሊኒ ያደረጉት ስምምነት፣
- እንግሊዞች ያቀረቡት የዕርቅ ሐሳብ ምን እንደነበረ፣

በጣልያንና በፈረንሣይ የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴሮች አርሺቭ ከሚገኙት ሰነዶች ሌላ፣ በገኔቭ የቀድሞው የሊግ ኦፍ ኔሽን ጉዳይ በተከማቸበት መዝገብ ቤት ውስጥ በዝርዝር ማግኘት ይቻላል። ይኸውም፣

"Journal De Societe Des Nations" Document Nº 1615

## ሦስተኛው ክፍል፤

«የፈረደባት ኢትዮጵያ ለሰባት ወራት» በተባለው በዚህ በሦስተኛው የታሪክ ክፍል ውስጥ የተጻፈው፤

- ሙሶሊኒ ወሰን ጥሶ በኢትዮጵያ ላይ ጦርነቱን እንደጀመረ፣
- ኢትዮጵያ ባላት አቅም ለመከላከል እንደተገደደች፣
- የመንግሥታት ማኅበር ልዩ ስብሰባ አድርጎ በሙሶሊኒ መንግሥት ላይ የኢኮኖሚ ዕገዳ እንዳደረገ፣
- የንጉሠ ነገሥቱ የማይጨው ዘመቻ፣
- ተቀባይነት ያላገኘው የፈረንሣይና የእንግሊዝ የዕርቅ ፕላን፣
- ንጉሠ ነገሥቱ በጄኔቭ ሸንጎ ላይ ተገኝተው ያቀረቡት አቤቱታ፣
- ታሪካዊው የመንግሥታት ማኅበር ዳኝነትና ፍርድ፣
- ኢትዮጵያ በፋሽስት እጅ!
- የእንግሊዞች፣ የፈረንሣዮችና የቫቲካን አቋም .......

ከእነዚህ ከተዘረዘሩት ዋና ዋና ጉዳዮች ውስጥ፤

1ኛ/ የንጉሠ ነገሥቱ የማይጨው ዘመቻ የተጻፈው፤ በዚያን ዘመን የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ጸሐፊ የነበሩት አቶ ገብረወልድ እንግዳወርቅ ባቀረቡት የታሪክ ማስታወሻ መሠረት ነው። ይህንንም የማይጨው ዘመቻና የጉዞው ታሪክ በሚል የተዘጋጀውን ሰነድ፤ አሁን በቅርቡ የአዲስ አበባ ዩኒቨርሲቲ ፕሬስ በድጋሚ አሳትሞ እንዲሰራጭ አድርጎታል።

2ኛ/ በኢትዮጵያ ጉዳይ የቫቲካን አቋም እንዴት እንደነበረ፤ የዚህ መጽሐፍ ደራሲ ዘርዝሮ ለመጻፍ የቻለው፤ አሁን በቅርቡ ሮም የሚገኘው መንበረ ጴጥሮስ፤ ከዛሬ አምሳ ዓመታት በፊት ስለነበረው የቫቲካን አሠራር ታሪክ ለታወቁ ተመራማሪዎች የከፈታቸውን የምሥጢር ሰነዶች ለማጥናት ዕድል ስለገጠመው ነው።

Archivo Segreto Vaticano santa Sede E Conflito Italo-Etiopico Da Vol I,II,III,IV,V,VI.

ሌሎቹ በዚህ በ3ኛው ክፍል የቀረበው ታሪክ፤ በእንግሊዝ አገር «Public Record Office» እና በፓሪስ «Quai d'orsay» ካሉት ሰነዶች ሌላ፤ በጄኔቭ የቀድሞው የሊግ ኦፍ ኔሽን ዶክመንቶች በተከማቹበት በ «Palais-Des Nations» መረጃዎቹ ሁሉ የሚገኙ መሆናቸውን ደራሲው ለተመራማሪዎች ይገልጻል።

## አራተኛው ክፍል፤

አውሮፓ ወደ ሁለተኛው የዓለም ጦርነት ሲጓዝ፤ የኢትዮጵያ ዕድል ምን ይሆን? በሚል ርዕስ፤ በስድስት ምዕራፎች ተደልድለው የቀረቡት ጉዳዮች መሠረታዊው ዓላማቸው፤

1ኛ/ አዶልፍ ሂትለር የጀርመን ባለሙሉ ሥልጣን መሪ ለመሆን የበቃበትን መንገድና፤ ወደ ሁለተኛው የዓለም ጦርነት እንዴት እንዳመራ፣

2ኛ/ የእንግሊዝና የፈረንሣይ መንግሥታትም ሳይዘጋጁ ሂትለር በፍጥነት ጦርነት እንዳያነሳባቸው ለመለማመጥ፤ የኦስትሪያንና የቼኮስሎቫኪያን ነፃነት ያለ አንዳች ችግር እንደገበሩለት፣

3ኛ/ ሙሶሊኒ ከሂትለር ጋር እንዳይቀራረብ እያባበሉ ለማቆየት፤ እንግሊዝና ፈረንሣይ ከሦስት ዓመት በፊት የኢትዮጵያን ነፃነት «መስዋዕት» ካደረጉለት በኋላ፤ ከዳተኛው ፋሽስት ከናዚስቱ ጋር ተሰልፎ እንዴት እንደወጋቸው፣

4ኛ/ የሁለተኛው የዓለም ጦርነት እየተፋፋመ በመሄድ፤ የሂትለር ኃይል የፈረንሣይን ነፃነት በጥቂት ጊዜ ውስጥ ከገፈፈና አገሪቱን ከያዘ በኋላ፤ ታላቋ ብሪታንያ በቆራጥነት ብቻዋን የናዚስትንና የፋሽስትን ጦር እንደመከተች፤ ጠቅላላውንና ትክክለኛውን ሥዕል ለማስረዳት የተዘጋጁ ናቸው።

የዚህን የሁለተኛውን የዓለም ጦርነት አነሳስና አካሄድ የኢትዮጵያንም ጉዳይ ችላ ሳይሉ በሰፊው የጻፉት ብዙዎች ደራሲዎች ስለሆኑ፤ ዝርዝራቸውን ለመደርደር ቦታ አይበቃም። ሆኖም የዚህ መጽሐፍ ደራሲ በታሪክ አቀራረባቸውና ሐቀኛነታቸው እጅግ የሚያደንቃቸውን ሁለት ታላላቅ ጸሐፊዎች ለተመራማሪዎች ይጠቅሳቸዋል። እነዚህም፤

1. **Pierre Renouvin**
   Histoire Des Relations Internationales
   Tome Septieme
   De 1914 a' 1945 (Edition Hachette)

2. **J.B. Duroselle**
   Histoire Diplomatique
   De 1919 a' 1970 (Edition Dalloz)

## አምስተኛው ክፍል፤

«የተበደለች ኢትዮጵያ ፀሎቷ ተሰማ» በሚል ርዕስ የተጻፈው ጉዳይ፤ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት መሪዎች ፊታቸውን ወደ ኢትዮጵያ በመመለስ፤ የፋሽስትን ጦር ከአገራችን ለማባረርና ነፃነታችንን እቦታው ለመመለስ እርምጃ ወስደዋል በማለት ነው። እርግጥ ነው! ይህ የተጠቀሰው ሐሳብ በመጨረሻ መፈጸሙ ባይቀርም፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ከሱዳን ተነስተው አዲስ አበባ ለመግባት እስከቻሉበት ቀን ድረስ፤ ለአሥር ወራት እንግሊዞች ያደረሱባቸው ውስብስብ ችግር ከመጠን ያለፈ ነበር።

በዚህ መጽሐፍ ውስጥ የታላቋ ብሪታንያ ወታደራዊ ባለሥልጣኖች ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ሱዳን ከደረሱ በኋላ፤ አስፈላጊው የጦር ዝግጅት ተሰናድቶላቸው፤ አርበኞቻቸውን ይዘው በፋሽስት ላይ በመዝመት ከካኒግሐም በፊት በድል አድራጊነት አዲስ አበባ ለመግባት እንዳይችሉ ምን ያህል መሰናክል እንደፈጠሩባቸው በዝርዝር ተገልጿል። ይህንን የደረሰውን የሚያሳዝን ሁኔታ የዚህ መጽሐፍ ደራሲ ሰፋ አድርጐ ለመጻፍ የቻለው፤ ከአንዳንድ ታላላቅ ሰዎች ካገኛቸው መረጃዎች ሌላ፤ ቀጥሎ በተዘረዘሩት ሰነዶች በመጠቀም ነው። እነዚህም፤

1. ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ «ሕይወቴና የኢትዮጵያ እርምጃ» በተሰኘው የታሪክ ማስታወሻቸው፤ ሁለተኛው መጽሐፍ ከገጽ 177 እስከ 323 ድረስ የገለጿቸው ዋና ዋና ጉዳዮች፤

2. ኮሎኔል ኦርድ ዊንጌት ጃንሆይ አዲስ አበባ እንደገቡ፤ ካይሮ ላይ ለሚገኘው ለታላቋ ብሪታንያ የመካከለኛው ምሥራቅ ጦር ዋና አዛዥ፤ ስለ ኢትዮጵያ ዘመቻ ተንትኖ ያቀረበው ብርቱ ምሥጢር የሆነ ትልቅ ራፖር ነው።

ዊንጌት ለበላዮቹ ወታደራዊ ባለሥልጣኖች ባቀረበው ራፖር፤ ለኢትዮጵያ ዘመቻ የተቋቋመው የጌዴዎን ጦር፤ ያለ በቂ ድርጅትና ያለ በቂ መሣሪያ ከመሆኑም በላይ፤ ከፋሽስት ጋር በገጠመው ውጊያ የጠየቃቸው ከባድ መሣሪያና የአየር ኃይል ድጋፍ ሳይሰጠው በመቅረቱ፤ ገጥሞት የነበረውን ከባድ ፈተና በዝርዝር ጽፎ ምሬቱን ለአለቆቹ በሰፊው ገልጿል። በተለይም በሱዳንና በኬንያ ያሉት የእንግሊዝ የጦር አዛዦች፤ በንጉሠ ነገሥቱ የሚመራው የጌዴዎን ኃይል ጀግኖቹን የኢትዮጵያን አርበኞች አስተባብሮ ፋሽስትን ድል በማድረግ አዲስ አበባ ለመግባት እንዳይችል፤ የፈጸሙትን በደል በድፍረት ደህና አድርጐ ስለአጋለጣቸው፤ የታላቋ ብሪታንያን የጦር መሪዎች ከፍ ያለ ብስጭት ላይ ጥሏቸዋል።

የመካከለኛው ምሥራቅ ጦር ዋና አዛዥ ይህ ሪፖረት እንደደረሰው፤ ኮሎኔል ዊንጌት የበላዮቹን በመዳፈር የሰነዘረብን ከባድ ነቀፌታ በቀላሉ መታለፍ የለበትም በማለት፤ በአስቸኳይ ወደ ካይሮ ተዛውሮ ለጌዴዎን ጦር



ብ/ጄኔራል ኦርድ ቻርል ዊንጌት፤ በኢትዮጵያ ነፃነት ጉዳይ የጌዴዎን ጦር አዛዥ ሆኖ እንደሠራው መልካም ሞያ፤ በበርማ ለተቀዳጀው ድል "የበርማው ዊንጌት" የተባለ መልካም ስም አስገኝቶለታል።

አዛዥነት ከተሰጠው የኮሎኔልነት ማዕረግ፣ ቀድሞ ወደነበረበት ወደ ሻለቃነት ደረጃ ዝቅ እንዲል ወሰነበት። ዊንጌት በዚህ በተደረገበት የቅጣት ውሳኔ እጅግ ከመበሳጨቱ የተነሳ፣ ሕይወቱን ለማጥፋት ሞክሮ፣ ለመዳን የቻለው በተዓምር ነበር።

ኦርድ ዊንጌት በዚያ በአስቸጋሪው የመከራ ዘመን፣ ለኢትዮጵያ ነፃነትና ለንጉሠ ነገሥቷ ደህንነት እስከሚቻለው ድረስ ያደረገው ተጋድሎና ያስገኘው ውጤት፣ ምንጊዜም በአገራችን ታሪክ የተከበረ ሥፍራ ሊሰጠው የሚገባው ነው። እነ ጀኔራል ዋቨልም ምንም እንኳ በዚያን ጊዜ ሥልጣኑ ተመችቷቸው በሐቀኛው መኰንን ላይ አግባብ የሌለው ቅጣት ቢበይኑበትም፣ በሁለተኛው የዓለም ጦርነት ምክንያት በእስያ ውስጥ «በርማ» በተባለው አገር ከባድ ችግር ሲደርስባቸው፣ ለዚህ ከባድ ግዳጅ ኃላፊነት ሰጥተው የላኩት ኦርድ ዊንጌትን ሆነ። ወዲያው ኦርድ ዊንጌት የጀኔራልነት ማዕረግ ተሰጥቶት፣ በጥቂት ጊዜ ውስጥ በርማ ላይ ያሳየው የጦር አመራርና በመጨረሻም የተቀዳጀው ድል በታሪክ ላይ «የበርማው ዊንጌት» የተባለ መልካም ስም አስገኝቶለታል።

ጀግናው ዊንጌት የሕይወት ታሪኩ በትክክል እንደሚያሳየው፣ በታዘዘበት ወታደራዊ ሚሲዮን ሁሉ መልካም ዝና ከማግኘት አላቋረጠም ነበር። መጀመሪያ በሱዳን፣ ቀጥሎ በፓሌስቲን ከዚያም በኢትዮጵያ የተሰጠውን ወታደራዊ ኃላፊነት ሲፈጽም፣ ኃይለኛና ደፋር ነው ከመባል በስተቀር፣ በወታደራዊ አመራሩና ብልህነቱ መልካም ዝና አልተለየውም። በመጨረሻም በተላከበት በበርማ ጦር ሜዳ ግዳጁን በመፈጸም ላይ እንዳለ፣ በአውሮፕላን አደጋ ሕይወቱ አለፈ። ቀዳማዊ ኃይለሥላሴና መንግሥታቸው፣ እንዲሁም ዊንጌትን ለማወቅ ዕድል ያጋጠማቸው የኢትዮጵያ አርበኞች ይህንን በጣም አስደንጋጭ ዜና ሲሰሙ፣ ኃዘናቸውን የገለጡት እጅግ በመረረ ስሜት ነበር።

ዊንጌት የኢትዮጵያ ዘመቻ ሲፈጸም ጽፎ ያቀረበው ሪፖርት፣ በዛሬው ሰዓት በእንግሊዝ አገር በ Public Record Office እና በ War Office ለተመራማሪዎች ተፈልጐ ሊገኝ አልቻለም። ይህም ሊገኝ ያልቻለው፣ ከአጻጻፉ ድፍረትና የጦር መሪዎቹን ጉድለት ደህና አድርጐ ከመግለጡ የተነሣ፣ ዶክመንቱ እንዲሠወር ስለተደረገ ነው ይባላል። የዚህ መጽሐፍ ደራሲ ግን በቀድሞው ዘመን ከቤተመንግሥቱ ጋር በነበረው ቅርበት፣ ዊንጌት ለጃንሆይ የሰጣቸውን የዚህን ሪፖርት ኮፒ አግኝቶ በወግ አስቀምጦት ነበር። አሁን የዚህ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መንግሥት ታሪክ ታትሞ ከወጣ በኋላ፣ ይህን ጠቃሚ ዶክመንት ደራሲው ለኢትዮጵያ ጥናትና ምርምር ተቋም ለመስጠት መወሰኑን ይገልጣል።

3. ዊልፍሬድ ቴሲገር፣ (Wilfred Thesiger) «The Life of My Choice» የመረጥኩት ሕይወት በሚል ርዕስ፣ ስለ ኢትዮጵያ ነፃነት ከካርቱም

እስከ አዲስ አበባ በተደረገው ዘመቻ፤ እሱ ራሱ የጊዴዎን ጦር አባል ሆኖ የተመለከታቸውን ሁኔታዎች ሁሉ ዘርዝሮ የጻፈው መጽሐፍ፤

4. አንቶኒ ሞክለር (Anthony Mockler) "የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ጦርነት" "Haile Selassie's War" በሚል ርዕስ በጻፈው አራት መቶ ስልሣ ገጾች ባሉት ትልቅ መጽሐፍ ውስጥ፤ በተለይ ለኢትዮጵያ ነፃነት የኢትዮጵያ አርበኞች የፈጸሙትን ተጋድሎ በዝርዝር የገለጸውን፤

5. ደጃዝማች ከበደ ተሰማ፤ ከሱዳን እስከ ኢትዮጵያ ዋና ከተማ ስለተደረገው የንጉሠ ነገሥቱ ዘመቻ የጻፉት የታሪክ ማስታወሻ፤

6. ከእንግሊዝ አገር «Public Record እና ከ War Office's» የተገኙ ዋና ዋና መረጃዎች፤

FO — 371-275 14
FO — 371-275 15
FO — 371-275 16
FO — 371-275 17
FO — 371-275 18
FO — 371-275 21
FO — 371-315 97
WO — 32 96 41

## ስድስተኛው ክፍል፤

በዚህ ክፍል ውስጥ የቀረበው ታሪክ ጣልያን ከኢትዮጵያ ከተባረረ በኋላ፤ እንግሊዞች አስገድደው የጫኑብንን የሞግዚት አስተዳደር የሚያስረዳ ነው። በዚህም ምክንያት ደራሲው "የእንግሊዞች ዘመን" ብሎ ሰይሞታል።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ከአምስት ዓመታት የስደት ሕይወት በኋላ በነፃነት አዲስ አበባ ሲገቡ፤ የእንግሊዝ ወታደራዊ ባለሥልጣኖች የአገሪቱን አስተዳደር ከፋሽስት ወርሰው የጠበቋቸው ባላሰቡት መንገድ ነው። ከሁሉ ይበልጥ ጃንሆይን በጣም ያሳዘናቸው፤ በእንግሊዞቹ አስተያየት "... የኢትዮጵያን ነፃነትና መንግሥት የማቋቋም ጉዳይ የሚወሰነው፤ ወደፊት የዓለም ጦርነት ተፈጽሞ የሰላም ጉባኤ በሚደረግበት ጊዜ ነው። እስከዚያ ጊዜ ድረስ ግን ኢትዮጵያ እንደ ሊቢያና ሱማሌ የጣልያን ኮሎኒ ሆና ትቆጠራለች" ተብሎ የተነገረው ነው።

በመሠረቱ፤ ጃንሆይ ከእንግሊዝ አገር ተነስተው ሱዳን ከመጡበት ጊዜ ጀምሮ፤ ጉጃም ገብተው ከዚያም አዲስ አበባ እስከገቡበት ቀን ድረስ፤ የእንግሊዝ ወታደራዊ ባለሥልጣኖች በሚያሳዩት አሠራርና ጠቅላላ ሁኔታ፤ ኢትዮጵያን በእነሱ ቁጥጥር ውስጥ ይዘው ለመቆየት እንጂ፤ ነፃነቷን ተቀብላ በቶሎ መንግሥቷን ለማቋቋም እንድትችል መርዳት እንደማይፈልጉ፤ ጃንሆይ ሳይጠረጥሩ አልቀሩም ነበር። ሆኖም እስከዚህ

ድረስ ንጉሠ ነገሥቱን ከሥልጣን አግልለው አገሪቱን በኮሎኒ መልክ ለማስተዳደር፣ እርምጃ ይወስዳሉ ብለው አልጠበቁም። ለዚህም የመጀመሪያ ማስረጃ የሆነላቸው፣ እንደ ኢት.አቆ. ግንቦት 2 ቀን 1933 ዓ.ም ንጉሠ ነገሥቱ በአዋጅ የሾሟቸውን ሰባት የካቢኔ ሚኒስትሮች፣ እንግሊዞቹ አንቀበልም ብለው ሹመቱን ሲያግዱ ነው።

እንግሊዞቹ የካቢኔውን መቋቋምና የሚኒስትሮቹን ሹመት አንስማማም ካሉ በኋላ፣ ለንጉሠ ነገሥቱ የነበራቸው ምርጫ የኢትዮጵያን ነፃነት ለማዳን በትዕግሥትና በዲፕሎማሲ ጉዳና መታገል ብቻ ነበር። በዚህም መሠረት ከእንግሊዝ ወታደራዊ ባለሥልጣኖች ጋር ያደረጓቸው ንግግሮች ሁሉ በዚህ በመጽሐፉ ስድስተኛው ክፍል ተዘርዝሮ እንደተገለጸው፣ ምንም እንኳ በጦርነቱ ምክንያት ዋና ዋናው የአስተዳደር ሥልጣን በወታደራዊው ኃይል ለተወሰነ ጊዜ ተይዞ መቆየት አለበት ቢባልም፣ "የኢትዮጵያ ነፃነት" በይፋ እንዲታወቅ የተደረገው ጥረት ውጤት አስገኝቷል። ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ እ.ኤ.አ ግንቦት 5 ቀን 1941 ዓ.ም አዲስ አበባ ከገቡበት ዕለት ጀምሮ፣ በኢትዮጵያና በታላቋ ብሪታንያ መካከል በግዴታ የተዘጋጀው ውል እስከተፈረመበት እስከ ጥር 30 ቀን 1942 ዓ.ም ድረስ፣ ከወታደራዊው ባለሥልጣኖች ጋር ያደረጓቸውን ድርድሮችና እንዲሁም በቤተመንግሥታቸው ስብሰባ እያደረጉ ከመሳፍንቶቹና ከሚኒስትሮቹ ጋር የተመካከሩባቸውን ጉዳዮች ደራሲው ማግኘት የቻለው፣ በዚያን ጊዜ የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር ከነበሩት ከአቶ ጌታሁን ተሰማ መሆኑን ለአንባቢዎቹ ይገልጻል።

ከእንግሊዞች ጋር ስለተፈረመው የመጀመሪያው ውል፣ ከሎንዶን የተገኙት መረጃዎች የሚከተሉት ናቸው።

FO -371-27524
FO -371-27522
FO -371-31597
FO -371-35611
FO -371-27525

እንደሚታወቀው፣ ይህ በወታደራዊው ባለሥልጣን አስገዳጅነት የተፈረመው የመጀመሪያው ስምምነት፣ የኢትዮጵያን አስተዳደር በእንግሊዞች እጅ ያደረገ ነበር። ይኸው ውል ከሚፈጸምበት ከሁለት ዓመት በኋላ፣ ለሚቀጥለው ስምምነት ይህ ዓይነቱ ሁኔታ እንዳይደገም፣ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መንግሥት ብርቱ ጥረት ሲያደርግና ሲዘጋጅ እንደነበረ፣ በመጽሐፉ ስድስተኛው ክፍል ውስጥ በሰፊው ተገልጿል። ለዚህ ጉዳይ በተለይ ከአሜሪካን መንግሥት ጋር በተቻለ ፍጥነት የዲፕሎማቲክ ግንኙነት መክፈት እጅግ አስፈላጊነቱ ስለታመነበት፣ የገንዘብ ሚኒስትሩ የአቶ ይልማ ዴሬሣ የዋሽንግተን ሚሲዮን ምን ያህል ፍሬያማ የሆነ ውጤት እንዳስገኘ፣ ጉዳዩን በዝርዝር ከሚያውቁት ከክቡር ጠቅላይ ሚኒስትር አክሊሉ ሀብተወልድ የተገኘው መረጃ የዚህን መጽሐፍ ደራሲ በጣም ረድቶታል።

በተጨማሪም፤ ደራሲው ዋሽንግተን በሚገኘው ናሽናል አርካይቭ (National Archives) ሄዶ ባደረገው ምርምር፤ አቶ ይልማ ዴሬሣ ከፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ዘንድ ለመቅረብና የኢትዮጵያን ጉዳይ ለማመልከት እንዴት እንደቀናቸው፤ ቀጥሎም ከስቴት ዲፓርትመንትና ከኮንግረስ አባሎች ጋር በመነጋገር ለኢትዮጵያ ጠቃሚ የሆኑ ጉዳዮችን እንደፈጸሙ ከዚህ ቀጥሎ የተጠቀሱትን ሰነዶች መርምሮ ለመረዳት ችሏል።

National Archives

884.00 Selassie-Haile/2-345
884.00 Selassie-Haile/1-2245
884.00 Selassie-Haile/1-1545
884.00 Selassie- Haile/2-545
884.00 Selassie-Haile/7-1443

እ.ኤ.አ በ1943 ዓ.ም ከአቶ ይልማ ዴሬሣ የዋሽንግተን ሚሲዮን በኋላ፤ በኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት መንግሥትና በዩናይትድ ስቴትስ ኦፍ አሜሪካ መካከል የተከፈተው የዲፕሎማቲክ ግንኙነት፤ ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ከፍ ያለ እርካታ ሰጥቷቸዋል። የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ወታደራዊ ባለሥልጣኖችም፤ የአሜሪካና የመስኮብ መንግሥታት በባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር ደረጃ የሚመሩ ለጋሲዮኖች አዲስ አበባ ላይ በመከፈታቸው፤ ታዛቢዎች አሉብን በማለት፤ በኢትዮጵያ አስተዳደር ጉዳይ ላይ ቀድሞ የሚያደርጉትንና የሚያሳዩትን የበላይነት መንፈስ መቀነስና ማለስለስ ግዴታ ሆነባቸው። የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ሚኒስትሮችም ሞራላቸውን በማጠንከር ስለ ሁለተኛው ውል ድርድር ጉዳይ፤ በተከበረው ኧርል ሎርድ ደላዋር (Earl Lord De La Warr) ከሚመራው ከታላቋ ብሪታንያ መልዕክተኞች ጋር፤ የኢትዮጵያን ነፃነትና ክብር ለማስጠበቅ ያደረጉት ሙግት የሚያኮራ ብቻ ሳይሆን፤ የሚያረካም ውጤት ለማስገኘት ችለዋል። ስለዚህ ስለ ሁለተኛው ውል ዝግጅትና አፈጻጸም፤ የዚህ መጽሐፍ ደራሲ ጉዳዩ በቀጥታ ከሚመለከታቸው ከክቡር አቶ አክሊሉ ሀብተወልድ በዚያን ዘመን የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ባገኛቸው መረጃዎች፤ በመጽሐፉ ስድስተኛው ክፍል ውስጥ በሰፊው ገልጾታል። በተጨማሪም ደራሲው እንግሊዝ አገር ሄዶ በ Public Record Office ባደረገው ምርምር የሚከተሉትን ሰነዶች ለማጥናት ችሏል።

FO -371/41454
FO -371/41455
FO -371/41457
FO -371/46052

# የቀዳማዊ ኃይለሥላሴና የሩዝቬልት ግንኙነት

በዚህ መጽሐፍ ስድስተኛው ክፍል ውስጥ በሰፊው እንደቀረበው፤ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥትና የአሜሪካ ፕሬዚዳንት ተገናኝተው ለመነጋገር እንዲችሉ ከሁለት ዓመት በበለጠ ጊዜ ጥረት ተደርጎበታል።

ማንም ሰው በቀላሉ እንደሚገምተው፤ በሁለቱ መሪዎች መካከል ለሚደረገው ንግግር፤ ባለጉዳዩ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ናቸው እንጂ የአሜሪካው ፕሬዚዳንት አልነበረም። እ.ኤ.አ በታህሣሥ 1943 ዓ.ም ብላታ ኤፍሬም ተወልደመድህን በአሜሪካ የመጀመሪያው የኢትዮጵያ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር፤ በዋይት ኃውስ የሹመት ደብዳቤያቸውን ባቀረቡበት ዕለት፤ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ባደረገው ንግግር " ... እስከአሁን ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን አግኝቼ ሳልተዋወቃቸው በመቆየቴ አዝናለሁ። አሁንም ወደፊት እኔ ወደ ምሥራቅ አገሮች ስጓዝ ወይም እሳቸው አሜሪካ መጥተው ለመነጋገር እንድንችል እስብበታለሁ ... » ሲል የወረወረው የዲፕሎማሲ ቃል መነሻ ሆኖ፤ ይህን ሐሳብ ለመፈጸም ሁለት ዓመት ከሁለት ወር ጊዜ ፈጀ። በእነዚህ በሁለት ዓመታት ጊዜ ውስጥ የሁለቱን መሪዎች ግንኙነት ለማዘጋጀት ምን ያህል ውጣ ውረድ እንደጠየቀ፤ በመጽሐፉ ስድስተኛው ክፍል ተተንትኖ ቀርቧል። በዘመኑ ጉዳዩ ከሚመለከታቸው የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ከፍተኛ ባለሥልጣኖች ከተገኙት መረጃዎች ሌላ፤ በዋሽንግተን ናሽናል አርካይብ ያሉት ሰነዶች የሚከተሉት ናቸው።

884 -001 Selassie Haile /3-745
884 -001 Selassie Haile /2-2745
884 -001 Selassie Haile /1-1844
884 -001 Selassie Haile /12-2244
884 -001 Selassie Haile /014-7-2043

## ሰባተኛውና ስምንተኛው ክፍሎች፤

በእነዚህ በሁለት ዋና ዋና ክፍሎች ውስጥ ተጽፈው የቀረቡት፤ በቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ዘመነ መንግሥት የሥልጣን ዝናቸው እጅግ ስለታወቀው ስለ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስና፣ ስለ አቶ መኰንን ሀብተወልድ ጉዳዮች ነው። ይኸውም፤

1ኛ/ የእነዚህ የሁለት ሰዎች የየግላቸው አነሳስና ለከፍተኛ ሥልጣን ደረጃ የበቁት በምን አኳኋን እንደሆነ፣

2ኛ/ ሁለቱ ሰዎች በወዳጅነት ተሳስረው በንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት ዘንድ የያዙት የሥልጣን ኃይልና ትብብር እስከምን ድረስ እንደነበረ፣

3ኛ/ « አጅሬ » እየተባሉ የሚጠሩት የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ሥልጣን እየገሰገሰ ከጉልላቱ ሲጠጋ፤ በቤተመንግሥቱና በንጉሣዊው ቤተሰብ ዘንድ የፈጠረው ሥጋት እስከየት እንደአደገ፣

4ኛ/ ንጉሠ ነገሥቱ የሁለቱን ባለሟሎቻቸውን ወዳጅነት ለያይተው፤ «አጅሬ ወልደጊዮርጊስን» ከሥልጣን በመሻር የወሰዱት እርምጃ አፈጻጸሙ እንዴት እንደነበረ፤

በሰፊው ለማስረዳት ደራሲው ብዙ ጥረት አድርጐበታል።

የእነዚህን የሁለት ታላላቅ ሰዎች ሙሉ የሕይወት ታሪክ ለመሰብሰብ፣ ደራሲው ከሁለቱም ቤተሰቦች ከፍ ያለ ትብብር ማግኘቱን ለአንባቢዎቹ ይገልጻል። ስለ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ፤ እ.ኤ.አ በኅዳር 1992 ዓ.ም በአዲስ አበባ ዩኒቨርሲቲ ከአቶ መኰንን ተገኝ ከተደረገው ምርምርና ጥናት ሌላ፤ ልጆቻቸው ወይዘሮ መዓዛ ወልደጊዮርጊስ እና ልጅ አስፋ ወልደጊዮርጊስ ያላቸውንና የሚያውቁትን መረጃዎች በመለገስ ደራሲውን ረድተውታል።

ስለ አቶ መኰንን ሀብተወልድ፤ የአክስታቸው ልጅ የሆኑትና አብሮ አደጋቸው፤ - ደጃዝማች ታከለ ወልደሐዋርያት፣
- ቤተዘመድ የሆኑት ደጃዝማች ማሀሉ ድፋዩ

በመንግሥቱ ንዋይ ኩ ዴታ አቶ መኰንን ከተገደሉ በኋላ፤ የአርባ ቀን መታሰቢያቸው ሲከበር የሰጡትን ዝርዝር የሕይወት ታሪክ መረጃዎች፤ ደራሲው ተጠቅሞበታል።

ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና አቶ መኰንን ሀብተወልድ፤ የጃንሆይ ፍጹም ታማኞች በመሆን በንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት አመራር ላይ ስለነበራቸው ከፍተኛ የሥልጣን ኃይልና በመካከላቸውም ስለተሳሰረው ወዳጅነትና አንድነት፤ በዚያን ዘመን የመንግሥት ዋና ዋና ኃላፊዎች ሆነው የሠሩት ሰዎች፤ ደራሲው በተለያየ ጊዜ ላቀረበላቸው ጥያቄዎች ያዩትንና የሚያውቁትን በሚገባ ገልጸውለታል።

## ሀ/ ስለ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ የሥልጣን አመራርና አፈጻጸም ደራሲው ያነጋገራቸው፤

1. በፍርድ ሚኒስቴር የጸሐፊ ትዕዛዝ ምክትል ሚኒስትር የነበሩት ኮሎኔል ታምራት ይገዙ፣

2. የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ጸሐፊና፤ ከጸሐፊ ትዕዛዙ ቀጥሎ ዋናውን ማሕተም ይይዙ የነበሩት፤ ቀኛዝማች ፊለቀ ዕርገቱ፣

3. የግርማዊነታቸው ዋና የእልፍኝ አስከልካይ በመሆን ለብዙ ዓመታት የሠሩት ኮሎኔል መኰንን ደነቀ፣ (ኋላ ብ.ጄኔራል)

4. የትምህርት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር የነበሩት አቶ በለጠ ገብረጻድቅ፣

ለ/ ስለ አቶ መኰንን ሀብተወልድ ሥልጣንና የአሠራር ጠባይ ደራሲው ያነጋገራቸው፤

1. በገንዘብ ሚኒስቴር የአቶ መኰንን ምክትል ሚኒስትር ሆነው ለዘጠኝ ዓመታት አብረዋቸው የሠሩት አቶ ምናሴ ለማ፣

2. ከንግሥተ ነገሥታት ዘውዲቱ ምኒልክ ዘመን ከ1911 ዓ.ም ጀምሮ፤ የአቶ መኰንን ሀብተወልድ ሕይወት እስከአለፈበት እስከ 1953 ዓ.ም ድረስ ለአርባ ሁለት ዓመታት አብረዋቸው የኖሩት ዘመዳቸው፤ ፊታውራሪ ሣህሉ ድፋዬ፣ (ኋላ ደጃዝማች)

3. ያሳደጓቸው ወንድማቸው አቶ መክብብ ዳምጤ፣

4. በገንዘብና በአገር ግዛት ሚኒስቴር፤ የአቶ መኰንን ሀብተወልድ የልዩ ጽሕፈት ቤት ሹም ሆነው በቅርብ የሠሩት አቶ አሰፋ ድፋዬ፣ (ኋላ የአዋሽ ሸለቆ ም/ሚኒስትር)

ሐ/ ስለ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና ስለ አቶ መኰንን ሀብተወልድ ወዳጅነትና የሥልጣን ዘመን፤ ደራሲው ካነጋገራቸው ታላላቅ ሰዎች መካከል ሦስት የካቢኔ ሚኒስትሮች የሚከተሉትን አስተያየቶች ሰጥተውታል፡፡

1. የሥራና የመገናኛ ሚኒስትር የነበሩት ብላቴን ጌታ ማሕተመሥላሴ፤ ስለ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ጠንካራ ሠራተኛነትና ወሳኝ መሪነት አድንቀው ሲናገሩ፤ አቶ መኰንን ሀብተወልድም ስለነበራቸው የአገር ፍቅር ስሜት ጠቅሰዋል፡፡ በመጨረሻ ስለ ሁለቱም ሰዎች ብላቴን ጌታ አስተያየታቸውን ሲያጠቃልሉ፤ « ... ሁለቱንም ጃንሆይ አቅርበው በሥልጣን ካሳደጓቸው በኋላ፤ ጊዜው ሲያበቃ የሁለቱም ወዳጅነት ፈርሶ አንዱን ከአጠገባቸውና ከሰጡት ኃላፊነት ሲያርቁ፤ ሌላውን ደግሞ አጠገባቸው ለማቆየት ሳደረጉት ውሳኔ፤ የራሳቸው ምክንያት ስለሚኖራቸው፤ እኛ በዚህ ጉዳይ ገብተን አስተያየት መስጠት አንችልም ... » ብለዋል፡፡

2. የሕዝብ ጤና ጥበቃ ሚኒስትር የነበሩት አቶ አበበ ረታ፤ እነዚህ ሁለት ታላላቅ ሰዎች ጠቅላላ ሁኔታቸው ሲጠና፤ በዕድሜ ብቻ ሳይሆን፤ በብዙ ረገድ በጠባይም፣ በአስተሳሰብም፣ በአኗኗርም በጣም የተለያዩ መሆናቸውን ለማወቅ አያስቸግርም ... ካሉ በኋላ፤ እነዚህ ሰዎች በመካከላቸው የመሠረቱት ወዳጅነትና የሥራ መደጋገፍ ለኢትዮጵያ ዕድገት በማሰብ ነው? ወይስ ለየግላቸው ጥቅም? ... ይህንን በጥልቀት መርምረው አስተያየታቸውን መስጠት የሚገባቸው፤ በእነሱ ዘመን የካቢኔ ሚኒስትር የነበሩት ሰዎች ናቸው፡፡ እኔ አበበ ረታ በዚያን ዘመን በዲፕሎማሲው ተግባር ለብዙ ዓመታት ውጭ አገር ስለነበርኩ፤ ለጥያቄው የተሟላ አስተያየት ልሰጥ አልችልም ብለዋል፡፡

3. <u>የሕዝባዊ ኑሮ ዕድገት ሚኒስትር የነበሩት አቶ ጌታሁን ተሰማ፣</u> ለደራሲው የሰጡት አስተያየት የሚከተለው ነበር።

« ... እኔ ዕድሌ ሆኖ በጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና በአቶ መኰንን ሀብተወልድ ብዙ ጥቃት የደረሰብኝ ሰው ነኝ። ይህንንም ዝርዝር ውስጥ ገብቼ በዚህ ተጐዳሁ! በዚህ ተጠቃሁ! ማለት አልፈልግም። ደግሞም ሁለቱም ሰዎች ጉዳት ያደረሱብኝ ናቸው በማለት፣ እነሱ ለአገራችን የሰጡትን አገልግሎት ለማቃለል የምፈልግ አይደለሁም። ሁለቱም በአንድነት የጃንሆይ የቅርብ ባለሟሎች ሆነው በሚሠሩበት ጊዜ፣ ብዙ ለአገር ጥቅም የሚሆኑ ተግባሮችን መፈጸማቸውን አምናለሁ። ይሁን እንጂ፣ እኔ ይሳሳቱ ነበር የምለው፣ አንዳንድ ይወደናል የሚሉትን ሰው እየመረጡ ለአግባብ በሥራ ማሳደጋቸውንና፣ አንዳንድ የሚጠሉትን ደግሞ ተከታትለው ማጥቃታቸውን ነው። ይህንንም ማድረግ የቻሉት ጃንሆይ ለሁለቱም የሰጧቸው ሥልጣን ስለተመቻቸው መሆኑ ጥርጥር የለውም። በተለይ ወደ መጨረሻው ዘመን በጸሐፊ ትዕዛዝ ላይ የሚታየው የሥልጣን ኃይል፣ እንኳንስ እኛን ሚኒስትሮቹን ይቅርና፣ ጃንሆይንም ሊያሠጋ እንደሚችል መገመት አያስቸግርም ነበር። የኋላ ኋላ የደረሰውም ይኸው ነው። ከዚህ ሌላ የምጨምረው የለኝም ... » ብለዋል።

<u>መ/ ስለ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ከሥልጣን መነሳት፣</u>

በዘውድ ምክር ቤትና በግርማዊት ቪላ በከፍተኛ ምሥጢር ይካሄድ ስለነበረው ስብሰባ፣ ያዩትንና ያወቁትን ለዚህ መጽሐፍ ደራሲ የነገሩት በዚያን ጊዜ የገነተ ልዑል ቤተመንግሥት ባልደረቦች የሚከተሉት ናቸው።

1. <u>በጅሮንድ ገዛኸኝ ገብረማርያም</u>፣ የግርማዊት እቴጌ ዋና የግምጃ ቤት ሹምና የምሥጢር ማስታወሻ ያዥ፣

2. <u>ብሪጋድየር ዤኔራል መኰንን ደነቀ፣</u> የቀ.ኃ.ሥ ዋና የእልፍኝ አስከልካይ፣

3. <u>ቀኛዝማች ፋንታዬ ጅማ</u> (የአባ ሐና ወንድም) የጃንሆይ ዋና የእልፍኝ አሽከር፣

4. <u>አቶ አያሌው ይመር፣</u> የግርማዊት እቴጌ ምክትል የእልፍኝ አስከልካይ፣

<u>ሠ/ ስለ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ሥልጣንና ሽረት ጠቅላይ ሚኒስትር አክሊሉ ሀብተወልድ ለደራሲው በሰፊው የሰጡትን ኢንተርቪው መመልከት ብዙ ነገሮችን ያብራራል።</u>

# ምሥጋና


ክቡር አቶ አሰፋ ድፋዩ
የአዋሽ ሸለቆ ባለስልጣን ሥራ አስኪያጅ

ክቡር አቶ መኰንን ሀብተወልድ መጀመሪያ የገንዘብ፣ ቀጥሎ የአገር ግዛት፣ በመጨረሻም የንግድ፣ የኢንዱስትሪና የፕላን ሚኒስትር በነበሩበት ዘመን፣ የልዩ ጽሕፈት ቤታቸው ሹምና የቅርብ ረዳታቸው በመሆን፣ እስከ ሕይወታቸው ፍጻሜ ሳይለያቸው የሠራ ነው።

ወዳጄ ወንድሜ አቶ አሰፋ በማስታወቂያ ሚኒስቴር በምሠራበት ጊዜ፣ ስለ አገራችን ዘመናዊ ታሪክ እንድከታተል፣ በተለይም በቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መንግሥት ውስጥ የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስንና የአቶ መኰንን ሀብተወልድን የሥልጣን ዘመን እንድጽፍ አጥብቆ ያተጋኝ ነበር። ስለዚህም፣ በጉዳዩ ላይ የሚያውቀውን ሁሉ በሚገባ አስጠንቶኛል።

አቶ አሰፋ ድፋዩ ስለ እነዚህ ሁለት ታላላቅ ሰዎች በዚያን ዘመን ትክክለኛውንና እውነተኛውን ጉዳይ ገልጦ መጻፍ ወይም ማስረዳት ሳይቻል በመቅረቱ፣ በሕዝቡ ዘንድ ብቻ ሳይሆን የመንግሥት ኃላፊዎችና ሠራተኞች የሆኑትም ሁሉ፣ እርስ በርሳቸው በሚወያዩትና በሚሰጡት የተሳሳተ አስተያየት፣ ከፍ ያለ ኃዘን ይሰማው ነበር። እሱ ራሱ የአቶ መኰንን ሀብተወልድ ልዩ ጸሐፊና ልዩ ረዳት ሆኖ ለብዙ ጊዜ በመሥራቱ፣ በእነዚህ በሁለቱ ታላላቅ ሰዎች መካከል የነበረው የሥልጣን ትብብርና የተሟሠረ ወዳጅነት፣ የፈረሰበትንና የተለያየበትን ምክንያት ደህና አድርጎ ያውቃል። ነገር ግን የንጉሡ ነገሥቱ መንግሥት ኃላፊዎችና ሠራተኞችም ሆኑ የከተማው ሕዝብ፣ በአፍ ታሪክ የሚነዛውን ወሬ እየተከተሉ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን ከሥልጣን ያስነሱ፣ የጃንሆይ ባለሟልነቱንና ከፍተኛውን ሥልጣን ብቻቸውን የያዙ፣ አቶ መኰንን ሀብተወልድ ናቸው ብለው አምነዋል።

አቶ አሰፋ ድፋዩን እጅግ አድርጐ ያስገረመውና ያሳዘነው፣ ይህ ዓይነቱ የተሳሳተ አስተያየት ነበር። ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን የሚያህል ትልቅ ባለሥልጣን፣ ከወዳጃቸው ከአቶ መኰንን ሀብተወልድ ጋር ስላልተግባቡ ብቻ፣ ንጉሡ ነገሥቱ ሽረዋቸዋል ብሎ ማሰብና ማውራት ምን ያህል ደካማ አስተያየት መሆኑን አቶ አሰፋ ለማስረዳት ብዙ ጥረት አድርጓል። አንዳንድ ሰዎች ቀጥታ ሲጠይቁትም የሚሰጠው አጭር መልስ፣ " ... ጃንሆይ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን ከዚያ ከትልቁ ሥልጣናቸው ያነሷቸው፣ ለመኰንን ሀብተወልድ ሲሉ አይደለም። ወይም ደግሞ የመኰንን ሀብተወልድ ኃይል ጃንሆይን አሸንፎ ወልደጊዮርጊስን እንዲሽሩ አላስደረገም ... " በማለት ነበር።

እንግዲህ! አቶ አሰፋ ድፋዬ እኔን ደጋግሞ ይመክረኝና ያበረታታኝ የነበረው፣ የእነዚህን የሁለት ታላላቅ ሰዎች ጉዳይ፣ ከአድልዎ ፍጹም ነፃ በሆነ መንገድ ትክክለኛውን ታሪክ በዝርዝር በማጥናት መጻፍ አለብህ ብሎ ነው። እኔም ረጅም ጊዜ ወሰደብኝ እንጂ፣ አቶ አሰፋ የመከረኝንና ያተጋኝን ከግቡ ሳላደርስ የቀረሁ አይመስለኝም። ወንድሜ ወዳጄ በአረመኔው ደርግ ባይገደልና በሕይወት ቆይቶ ቢሆን ኖሮ፣ ይህንን አዘጋጅቼ ያቀረብኩትን መጽሐፍ በምን አኳኋን ይመለከተው ነበር? ብዬ አስባለሁ። ይሁን እንጂ፣ ያችን እየደጋገመ የመከረኝን "ከአድልዎ ነፃ በሆነ መንፈስ" የሚላትን ሐሳብ በተቻለኝ የተከተልኩና፣ በተቻለኝም እውነተኛውን ታሪክ የገለጥኩ መሆኔን ሳይቀበለው አይቀርም ነበር የሚል ተስፋ አሳድራለሁ። በጠቅላላው ስለ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና አቶ መኰንን ሀብተወልድ ጉዳይ ለመጻፍ እንድችል፣ ከወንድሜ ከአቶ አሰፋ ድፋዬ ያገኘሁትን እርዳታ ዘወትር የማስበው መሆኔን፣ ለቤተሰብና ለወዳጆች ብቻ ሳይሆን፣ ለአንባቢዎቼም መግለጽ እወዳለሁ።


ፕሮፌሰር መርዕድ ወ/አረጋይ

ከደርግ ዘመን ፍጻሜ በኋላ እ.ኤ.አ በ1993 ዓ.ም ለመጀመሪያ ጊዜ ከስደት ወደ አገሬ ስመጣ፣ የቀድሞውን የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት የቀዳማዊ ኃይለሥላሴን መንግሥት ታሪክ መጻፍ አለብህ ብሎ በብርቱ ያሳሰበኝ፣ ወዳጄ ወንድሜ ፕሮፌሰር መርዕድ ወልደአረጋይ መሆኑን የማስታውሰው ጥልቅ በሆነ ስሜት ነው።

"የኤርትራ ጉዳይ" የተባለውን መጽሐፍ በቅድሚያ ሳዘጋጅ፣ ቀጥሎም ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መንግሥት ታሪክ መግቢያ እንዲሆን "ተፈሪ መኰንን" የተሰኘውን ስጽፍ፣ የወዳጄ የፕሮፌሰር መርዕድ እርዳታ አልተለየኝም ነበር። እነዚህን ሁለት መጻሕፍቶች ጨርሼ ለአንባቢዎች ካቀረብኩ በኋላ፣ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴን መንግሥት ታሪክ መጻፍ ስጀምር የሰጠኝን የማበረታቻ ምክር መቸውንም አልረሣውም።

" ... ዘውዴ! ከእኛ ጋር ተመሳሳይ ከሆነው ትውልድ መካከል፣ እንደ አንተ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴን መንግሥት አመራር በቅርብ የማየትና የመረዳት ዕድል ያገኘ ብዙ ሰው የለም። ቀጥሎ ደግሞ ያየውንና የተረዳውን፣ ጣዕም ባለው ጽሑፍ አብራርቶ ለመግለጽ ተሰጥዎ ያለው እንደ አንተ የመሰለ ጸሐፊ ብዙ የለም። ስለዚህ፣ በእኔ አመለካከት ሁለት የተጣመሩ ዕድሎች በአንተ እጅ ተይዘው ይገኛሉ። እነዚህም ታሪኩን የማወቅና የጽሕፈት ችሎታህ ናቸው። ስለዚህ እኔ አጥብቄ አደራ የምልህ፣ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴን መንግሥት ጉዳይ አንተ ዕድል አጋጥሞህ ያየኸውንና፣ ከአዋቂዎች ዘንድ ቀርበህ ያጠናኸውን፣ እውነተኛውን ታሪክ ገልጠህ ለኢትዮጵያ ሕዝብ ጻፍለት። ለዚህ ሕዝብ ከአንተ በኩል ከዚህ

የበለጠ የምታደርግለት ሊኖር አይችልም። አንተም አስበህ የጀመርከውን ለመፈጸም እግዚአብሔር ይርዳህ። ... እኛም ወዳጆችህ፣ ዕድሜና ጤና አግኝተን የምትደክምበትን ለማንበብ ያብቃን ... " ሲል ልባዊ ስሜቱን ገልጸልኝ ነበር።

ወንድማችን መርዕድ ይህንን ጥልቅ ምኞት የገለጸልኝ፣ ከዚህ ዓለም ከመለየቱ ከአንድ ዓመት በፊት ነበር። እንደተመኘልኝ በእግዚአብሔር ቸርነት እኔ መጽሐፉን ጨርሼ ለማቅረብ በቃሁ። ነገር ግን እኔም ተመኘቼ እንደነበረው ወዳጄ መርዕድ በሕይወት ቆይቶ የድካሜን ፍጻሜ ለማየት ባለመቻሉ፣ እጅግ አድርጌ አዝናለሁ። ሆኖም እኔም በተራዬ እንደሱ ተጠርቼ እስከምከተለው ድረስ፣ የዚህን ትልቅ የተከበረ ጨዋና ደግ ሰው ነፍስ እግዚአብሔር ይማርልን እያልኩ ውለታውን ዘወትር የማስብ መሆኔን ለቤተሰቦቹና ለአንባቢዎቼ የምገልጸው ጥልቅ በሆነ ስሜት ነው።

## 3. አቶ ደህኔ ረታ

ከዚህ ቀደም "የኤርትራ ጉዳይና ተፈሪ መኰንን" የተሰኙትን ሁለቱን መጽሕፍቶች በማዘጋጅበት ጊዜ፣ ወንድሜ አቶ ደህኔ ረታ ምን ያህል እንደረዳኝ ለአንባቢዎቼ የገለጥኩትን አስታውሳለሁ። አሁንም ይህንን የቀዳማዊ ኃይለሥላሴን መንግሥት ታሪክ ሳዘጋጅ፣ ባለፉት መጻሕፍቶቼ እንደደከመልኝ ሁሉ ሰነዶችን በመመርመርና አስፈላጊዎቹን እየለዩ በመምረጥ፣ ሥነ ጽሑፎቹን በማስተካከልና ጠቃሚ የሆኑ ሐሳቦችን በመስጠት፣ ወንድሜ አቶ ደህኔ ላደረገልኝ እርዳታ የማቀርብለት ምሥጋና እጅግ የላቀ መሆኑን እገልጻለሁ።

## 4. ቤተሰቦቼ

የዚህን መጽሐፍ ዝግጅት ከጀመርኩበት ጊዜ አንስቶ እስከ ፍጻሜው ድረስ፣ ለጤናዬ በማሰብ፣ ለሥራዬም መልካም ውጤት በመመኘት ያልተለዩኝን ቤተሰቦቼን፣ ባለቤቴ ወይዘሮ ገሊላ ተፈራን፣ ልጆቼን ዶክተር አያልነሽን፣ ወ/ት ቤተልሔምንና ልጅ ገብርኤል ረታን ከእኔ ጋር እንኳን ደስ ያላችሁ እላቸዋለሁ።

## 5. ለመጽሐፉ ዝግጅትና ሥርጭት ልዩ ልዩ እርዳታ የሰጡ

1. ልጅ የወንድወሰን መንገሻ
2. ኢንጂኒየር ተረፈ ራስወርቅና ባለቤታቸው ወ/ሮ ብርሃኔ አስፋው
3. አቶ አረጋ ወርቁ ተሰማ
4. አቶ የማነ ብሥራት ሀብተማርያም
5. አቶ ሞሐመድ ኢብራሂም /ሎሳንጀለስ/

## 6. በዶክመንትና በፎቶግራፍ አሰባሰብ የረዱ

1. ክቡር ደጃዝማች ብርሃነ መስቀል ደስታ፣ /ሎሳንጀለስ/
2. ፕሮፌሰር ንጉሤ አየለ፣ /ከካሊፎርኒያ ዩኒቨርሲቲ/
3. ፕሮፌሰር ሽፈራው በቀለ፣ /ከአዲስ አበባ ዩኒቨርሲቲ/
4. ፕሮፌሰር ጥላሁን ተሾመ፣ /ከአዲስ አበባ ዩኒቨርሲቲ/
5. አቶ የማነ እጅጉ፣ /ኒውዮርክ/
6. ልጅ ጉበና ወርቁ፣ /ሎንዶን/
7. ወይዘሮ ውልታ መካሻ፣ /ሎንዶን/

## 7. የቴክኒክ እርዳታ የሰጡ

1. የመጽሐፉን ሥነ ጽሑፍ፣ ግድፈቶቹን በማስተካከልና ፊደሎቹን በማረም ከፍ ያለ እርዳታ የሰጡኝን ወዳጄ አቶ መላኩ ደገፉን አመሰግናቸዋለሁ።

2. በዚህ መጽሐፍ ውስጥ የሚገኙትን ብዙዎቹን ፎቶግራፎች፣ ከልዩ ልዩ ሰነዶች ላይ በመቅረጽና በማተም የረዱኝን የቪዲዮ ፎቶ አምባሳደር /Video Photo Ambassador/ ባለቤት አቶ ግርማይ ካህሣይን ከልብ አመሰግናለሁ።

3. የመጽሐፉን ሽፋን /Cover/ በቴክኒክ አቀናብሮ ያዘጋጀልኝን ወንድሜን አቶ ንጉሤ አካለወርቅን አመሰግናለሁ።

4. ይህንን መጽሐፍ ሳዘጋጅ፣ ለስድስት ዓመታት የኮምፒውተር ጸሐፊዬ ሆና ቀልጣፋና ደስ የሚያሰኝ ተግባር ለፈጸመችው ለወ/ሮ ሊሊ ለገሠ የጋለ ምሥጋናዬ እንዲደርሳት ከልብ እመኛለሁ። ወ/ሮ ሊሊ ለገሠ ከዚህ ቀደም "የኤርትራ ጉዳይ" የተባለውን መጽሐፍ ሳዘጋጅ፣ በኮምፒውተር ጸሐፊነት ተግባር የሰጠችውን መልካም አገልግሎት በአድናቆት አስታውሳለሁ።

5. የመጽሐፉን ገጾች አቀማመጣቸውን በቴክኒክ ያቀናበራቸውና ፎቶግራፎቹን ላዋሐዳቸው የግራፊክ ዲዛይን ባለሞያ አቶ ዮሐንስ ገዛኸኝ ለፈጸመው መልካም ተግባር ደራሲው ከልብ ያመሰግነዋል።



ለዚህ መጽሐፍ ዝግጅት
የኢትዮጵያ አየር መንገድ
በትራንስፖርት በኩል ላደረገልኝ እርዳታ
ከፍ ያለ ምስጋና አቀርባለሁ፡፡



## የደራሲው አጭር የሕይወት ታሪክ

ዘውዴ ረታ፤ በኢትዮጵያ ዘመን አቆጣጠር ነሐሴ 7 ቀን 1927 ዓ.ም አዲስ አበባ ተወለደ።

**ከ1933 እስከ 1945 ዓ.ም**

ቀድሞ ደጃዝማች ገብረማርያም ይባል በነበረውና ኋላ "ሊሴ ገብረማርያም" ተብሎ በተሰየመው የፈረንሣይ ትምህርት ቤት የመጀመሪያውንና የሁለተኛ ደረጃ ትምህርቱን አከናውኗል።

| | |
|---|---|
| ከ1945 እስከ 1948 ዓ.ም | በጋዜጣና ማስታወቂያ መሥሪያ ቤት፤ የቤተመንግሥት ዜና ጋዜጠኛና በራዲዮ ዜና አቅራቢ፣ |
| ከ1948 እስከ 1952 ዓ.ም | በፓሪስ የጋዜጠኝነት ሞያ በማጥናት በዲፕሎማ ተመረቀ፣ |
| ከ1952 እስከ 1954 ዓ.ም | የኢትዮጵያ ድምፅ ጋዜጣና የመነን መፍሔት ዲሬክተር፣ |
| ከ1954 እስከ 1955 ዓ.ም | የኢትዮጵያ ራዲዮ የብሔራዊ ፕሮግራም ዲሬክተር፣ |
| ከ1955 እስከ 1958 ዓ.ም | የኢትዮጵያ ወሬ ምንጭ ዋና ዲሬክተር፣ |
| ከ1958 እስከ 1960 ዓ.ም | የማስታወቂያ ሚኒስቴር ረዳት ሚኒስትር፣ |
| ከ1960 እስከ 1962 ዓ.ም | የኢትዮጵያ ዜና አገልግሎት ድርጅት ዋና ሥራ አስኪያጅ፣ |
| ከ1956 እስከ 1962 ዓ.ም | የፓን አፍሪካ ኒውስ ኤጀንሲ ማኅበር ፕሬዚዳንት፣ |
| ከ1962 እስከ 1967 ዓ.ም | ወደ ውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ተዛውሮ፤ |

ሀ. በፓሪስ የኢትዮጵያ ኤምባሲ ሚኒስትር ካውንስለር፣
ለ. የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ም/ሚኒስትር፣
ሐ. በሮም እና በቱኒዚያ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት አምባሳደር ሆኖ ሠርቷል።

በጠቅላላው በቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ዘመነ መንግሥት የሀያ ሁለት ዓመታት አገልግሎት ካበረከተ በኋላ፤ በደርግ ዘመን ከ1967 ዓ.ም ጀምሮ ስደተኛ ሆኖ በአውሮፓ በቆየበት ዘመን፤ በሮም የኢንተርናሽናል ድርጅት ውስጥ (IFAD) ለአሥራ ሦስት ዓመታት በፕሮቶኮልና በመንግሥታት ግንኙነት ጉዳይ ኃላፊ ሆኖ ሠርቷል።

በ1959 ዓ.ም ጋብቻውን መሥርቶ፤ ከሕግ ባለቤቱ ከወይዘሮ ገሊላ ተፈራ ጋር ሦስት ልጆች አፍርተው ይኖራሉ። ከንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት የምኒልክ የመኮንን ደረጃና የኢትዮጵያ የክብር ኮከብ አዛዥ መኮንን ኒሻን ተሸልሟል። እንዲሁም ከአፍሪካ፣ ከእስያና ከአውሮፓ በድምሩ ከሀያ ሁለት አገሮች የታላቅ መኮንን ደረጃ ኒሻኖች ተሸልሟል። ከዚህ ቀደም በ1945 እና በ1946 ዓ.ም ካዘጋጃቸው አራት ቲያትሮች ሌላ፤ በ1992 ዓ.ም "የኤርትራ ጉዳይ" በ1997 ዓ.ም "ተፈሪ መኮንን" የተሰኙትን መጻሕፍቶች ጽፏል።